

# ራዕይ




ቅፅ 1 ቁጥር 2 ሐምሌ 1997 ዓ.ም



## ድንግልና ውበት ፡ ክብራችን ጤናም ጭምር ነው

አምባሳደር ዘመን ተፈራ



## ውስጣዊ ውበትን ያየሁት በስለሺ የተካሰ ነው

ወሰን ብርሃኑ (የጋሽ አበራ ሞላ ባለቤት)



## ኢንተርናሽናል ጆብ ማርኬት ያለው SOIL & WATER ENGINEERING ነው

ዶ/ር ጠና አላምረው (የትምህርትና ምርምር ም/ፕሬዝዳንት)

ANNE GEDDES

If you get more than one chance, try again

Prize your good ideas

Try not to make mistakes

And if you do,

learn from them

But in HIV, learning from own mistake is impossible rather others learn from your mistake........



SHDI

*Remedan Kasim*
*Kebede Gudissa*
*Abdulkerim Abarago*
*Yeshewareg Feyissa*
*Berissa Abdella*
*Yenenesh Hailu*
*Tirmubet Workineh*
*Adugna Tafesse*
*Daniel Getahun*

# አምዶቻችን




*Sponsored by*
*Self Help Development International*
*Alemaya project*


*Tel- 251-5-610706*
*E-mail- Shdialem@ethionet.et*






ኢብራሒም ሰይድ

## የአዘጋጁ መልክት

ትምህርት የስልጣኔ፡ የዕድገትና የብልፅግና ዋነኛ ቁልፍ ለመሆኑ ሁሉም የሚስማማበት ሀቅ ነው ። ይሄ እውነታ ግን እኛ ሀገር በመርህ ደረጃ ከመቀመጡ ውጭ አንዳች ገቢራዊ ፋይዳን ሲያንፀባርቅ አልታየም ። ይባስ ብሎ ትምህርት የመንግስትን እጅ ለመጠበቅ እንደአንድ ቅድመ ሁኔታ መቆጠር ከጀመረ ውሎ አድሯል ። እንደሚታወቀው የሐምሌ ወር በአብዛኛው ተማሪ የሚመረቅበት ፡የልፋቱን ውጤት የሚረከብበት በአጠቃላይ የድልም የተስፋም ወር ነው ። ውጭ ወጥቶ በተማረው ሞያ አዳዲስ ግኝቶችን እየፈጠረ እስከአላስተማረ ፡ አገሩንና ወገኑን እስካረዳ ድረስ አንድ ሰው ጥቁር ጋውንና ቆብ ስለደፋ ፡ዲግሪና ዲፕሎማም ስለተቀበለ ብቻ ተመረቀ ማለት አይቻልም ። ከዩኒቨርቲው ውጭ ወጥቶ የመንግስትን እጅ ከጠበቀ እጅና እግሩን አጣጥፎ ከተቀመጠ ይሄ ተመረቀ ሳይሆን ተረገመ ነው የሚባለው። መንግስትም ቢሆን በተወሰነ አመት ብቻ አስተምሮ አስመርቂያለሁ ለማለት ድፍረቱ ያለው አይመስለኝም ። ምክንያቱም ይሄ ብቻ በቂ አይደለምና! ከሕብረተሰቡ በግብር መልክ የሚሰበሰበውን ገንዘብ በደሞዝ ምልክ ከመክፈል ይልቅ ለስራ ፈጣሪነት የሚያነሳሱ የብድር አገልግሎትን ለተማሪዎች አመቻችቶ አገራችንን ማሳደጉ ላይ ነው ቁም ነገሩ ። ይሄ ሲሆን ነው ተማሪው ተመረቅኩኝ መንግስትም አስመረኩኝ ማለት የሚችለው ።

**congratulation**

<u>ዋና አዘጋጅ</u> ኢብራሒም ሠይድ

<u>ም/ዋና አዘጋጅ</u> ሳምሶን አብደላ

<u>ረዳት አዘጋጆች</u> አብዱልአዚዝ ዲኖ
ጌታቸው ዳውድ

<u>የኮምፒውተር ጽሑፍ</u> ቀለሚ በላይ
ማርታ አለምሸት

<u>የሽፋን ዲዛይን</u> ቤተልሔም ለገሰ
(ቀመር የጽህፈት መሳሪያ አገልግሎት-ሐረር)

<u>ሌይ አውት ዲዛይነር</u> -ኢብሮሰን(JQ-ENG)

<u>አድራሻ ዓለማያ ዩኒቨርሲቲ ፀረ-ኤድስ ንቅናቄ ራዕይ መጽሐት ዝግጅት ክፍል ✉ 138 ☎ 610509 -ዓለማያ</u>

<u>Email auaam97@yahoo. com -</u>



# እንግዳችን

ከአርስቲስት ስለሺ ደምሴ ( ጋሽ አበራ ሞላ ) ጎን ሁል ጊዜም ቢሆን የማትጠፋ ልጅ አለች :: ጋሽ አበራ ካለ እሷም አለች በአብዛኛው ያያቸው ሁሉ የእሷን ማንነት ለማወቅ የማያደርገው ጥረት የለም :: ሚስቱ ፣የስራው ባልደረባው ፣ እጮኛው ወዘተ ... ሁሉም የራሱን መላ ምት ይሰጣል :: ሲበዛ ቁምነገረኛ፣ እንደበተ ርቱእና ለስራ የተፈጠረች ዓይነት ናት - ወሰን ብርሃኑ :: የመፅሔታችን እንግዳ ልናደርጋት ነገርናት :: አላንገራገረችም ፤ተመቸችን :ተመቸናት :ተመቻችን የቃለ-ምልልሱን ሙሉ ክፍል እነሆ በረከት እንላለን ::

አዘጋጅ ኢብራሂም ሰይድ

## ውስጣዊ ውበትን ያየሁት በስለሽ የተነሳ ነው::

ወሰን ብርሀኑ

**ራዕይ:-** የትውልድ ቦታሽ የት ነው?

**ወሰን :-** የተወለድኩት አዲስ አበባ ሲሆን ልዩ ስሙ አምስተኛ ፖሊስ ጣቢያ ወይም ሜክሲኮ በቢባለው አካባቢ ነው::

**ራዕይ:-** የልጅነት ሂወትሽ በአጠቃላይ አስተዳደግሽ ምን ገጽታ አለው ?

**ወሰን :-** የልጅነት ሂወቴ የተለየ ነገር አልነበረውም:: ግን ቤተሰቦቼ ከፍተኛ ውጤት ላይ እንድደርስ ካላቸው ጽኑ ፍላጎት የተነሳ ለኔ ጥሩ አመለካከት ነበራቸው:: በተጨማሪ ታላላቅ እህቶቼም የኔን ጥሩ ከሚመኙት የቤተሰብ አባላት ዋንኞቹ ነበሩ:: እንደአጋጣሚ በዚህ ቦጋሽ አበራ ሞላ ፕሮጀክት ታቅፌ እየሰራሁ እገኛ ለሁ:: በዚህም በጣም ደስተኛ ሆኛለሁ:: ቤተሰቦቼም እንደዚሁ::

**ራዕይ:-** የትምህርቱ ነገርስ?

**ወሰን :-** በትምህርቴ ደህና ነበርኩኝ:: እንደአጋጣሚ ሆኖ አስረኛ ፈተና ወስደን ውጤት ሳይመጣ ቀረ:: ግን በተግባረድ ትምህርት ቤት 10+ 2 በ electricity ተመርቄአለሁ::

**ራዕይ:-** የወሰን የትርፍ ጊዜአት ስራዎቿ ወይም ሆቢዎች ምንድናቸው?

**ወሰን :-** ዲዛይነር ለመሆን ካለኝ ፍላጎት የተነሳ አቡጀዲዎችን እየቀደድኩኝ የእጅና የእግር ጨሌዎችን እሰራለሁ:: አሁን ግን በዚህ ፕሮጀክት ውስጥ ከታቀፍኩ አንስቶ እነዚህን ነገሮች ትቻቸዋለሁ:: ይሆን እንጂ በርካታ ቲሸርቶችን ፔይንት አድርጌ ቤት አስቀምጫቸዋለሁ:: አሁን አሊያዝኩዋቸውም እንጂ ባሳይህ ደስ ይለኝ ነበር::



**ራዕይ:-** ጋሽ አበራ ሞላ ወይም ከአርቲስት ስለሺ ደምሴ ጋር እንዴት ተገናኛችሁ?

**ወሰን :-** አክስቴውጭ ሐገር እወስድሻለሁ ስትለኝ የአገር ባህል ውዝዋዜ ተምሬ ብሄድ ይሻላል በማለት እሱ ውዝዋዜ ወደሚያስለጥንበት ወደ እስታዲየም አመራሁ ከዚያም ፋይናል ምረቃችን መቼ ነው ብዬ ልጠይቀው ስሄድ በዚህ አጋጣሚ ተያየን:: ከዚያም ተውውቃችን እየጠነከረ

በመምጣቱ እነሆ ዛሬ ለዚህ በቃን::

ራዕይ:- ጊዜውን ታስታውሸዋለሽ?

ወሰን :- የተዋወቅነው የአካባቢ ቀን ሲከበር ነው:: ግንቦት 28 1992 ዓ.ም:: ይኸው ስድስተኛ አመታችንን ይዘናል::

ራዕይ:- ወጣት በትኩስ ሐይል ይመሰላል አንቺም ወጣት ነሽና በአሁኑ ሰዓት ለሐገርሽ ምን እየሰራሽ ነው?

ወሰን :- ይህን እሰራለሁ ብሎ መጀመሪያላይ ቃል መግባት ቢያስቸግርም አትሊስት ከስለሺ ጋር ከተገናኘሁ አንስቼ በጣም በርካታ ነገር አስተምሮኛ ልና:: ለሐገሬ ብሎም ለህዝባችን የቻልኩትን ያህል በገንዘብ እንኳን መርዳት ቢያቅተኝ የምችላትን ነገር በጉልበቴ በዚህ ፕሮጀክት ውስጥ ከሱ ጋር እየሰራሁ እገኛ ለሁ::

ራዕይ:- በዚህ ስራ ምን ያህል ደስተኛ ነሽ ?

ወሰን :- ው . . ይ . በጣ. ም ልነግርህ አልችልም:: የጉዳና ተዳዳሪውን አንተ ቀርበኸው ችግሩን ተረድተህለት የቻልከውን ስታደርግለት በለውነቱ ፍቅርና አክብሮት ስትለግሰው እሱም የሂወት ቶሞክሮውን ሲገልጽልህ ያ ነው ላንተ ታላቅ satisfaction የሚሰጥህ: at least በቀን በአስራ ሁለት ብር ሂሳብ ሰላሳ አርባ ሰው ተጥረህ እነሡም እራሳቸውን እንዲችሉ ማድረግ ቀላል ነገር አይደለም በበኩሌ ደስታዬ ወደር የለውም::

ራዕይ:- የፕሮጀክታችሁ ስም ማን ይባላል?

ወሰን :- ጋሽ አበራ ሞላ አካባቢና ልማት ማህበር ነበረ አሁን ፕሮጀክት ብለነዋል::

ራዕይ:- አካባቢን ማስዋብ ቆሻሻን ማስወገድ እና ማጽዳት ውጤቱ እንጂ ጅማሮው ብዙም ብዙም ስለማይስብ ብዙሃኑ ያልደፈረው የበጉ አድራጉት ሥራ ነው ለመሆኑ የናንተ ፕሮጀክት ይህንን ሥራ ከምን አንፃር ሊጀምረው ቻለ? ያጋጠማችሁ መሠናክል /ቻሌንጅግስ/አለ ወይ?

ወሰን :- ይህንን የተጋነነ መሠናክል አላጋጠመንም ምክንያቱም ስለሺ በጣም ትዕግስተኛ ከመሆኑ የተነሣ ነገሮችን እንደ ቀላል ማለፍ ልማዱ ነው እኔን እራሡ ምን ያህል እንደለወጠኝ እኔ ነኝ የማቀው ጋሽ አበራ ሞላ አጉልቶ ተናገረው እንጂ ቆሻሻ የኢትዮጵያ ሕዝብ ችግር ነው:: በእያንዳንዱ ሠፈር ስትሄድ አፍንጫህን ይዘህ ነው የምታልፈው:: አዲስ አበባ ጉንደር: ደሴ: ባህር ዳር ድሬደዋ ምናምን ብትል አሁን ነው ለውጥ የመጣው ይሁን እንጂ ካለው ቆሻሻ አካባቢ አንፃር ስታይ የለውጡ እንቅስቃሴ ብዙም የሚያመጻድቅ አይደለም:: የሚገርምህ ነገር ግን ወጣቱ የሚደግፈው አጣ እንጂ ለሥራው ያለው ተነሣሽነት ቀላል አይደለም ወጣቱን የሚያሰራው ሰዉ አጣ እንጂ ትልቅ ለወጥ መፍጠር የሚያስችለው ሁኔታ ላይ ለመሆኑ ሁላችንም መመስከር እንችላለን በቆሻሻ አካባቢ መኖር ለሕይወት አደገኛ ነው ሥለዚህ ለሕይወታችን ሥንል: ለጤንነታችን ስንል እኛው የፈጠርነውን ቆሻሻ እኛው ማስወገድ እንዴት ያቅተናል:: ነጮች ኢትዮጵያ ውስጥ

**«እንደ ድሬደዋ ውብ እና የፀዳች ከተማ አላጋጠመኝም:: »**

መጥተው እኛን ስንፀዳዳ ፎቶ አንስተው ሲሄዱ ምን ያህል እንደሚያሣፍር ለምን አናስተውልም? የድህነቱስ ok ሌላ ጉዳይ ነው እንዴት መፀዳጃ ቤት ቆፍረን እንዴት አካባቢያችንን ከቆሻሻ አንታደጋትም:: እንሰማይቱ ድመት እኳ ሰው አየኝ አላየኝ ብላ አይደለም ከተፀዳዳች በኋላ አፈር አልብሣ የምትሄደው:: አሁን ግን ከእግዚአብሄር ጋር እየተለወጠ ነው በራፍህ ላይ አመድ:አተላና ሌሎችም መደፋቱ እየቀሩ ነው::

**ራዕይ:-** ቆሻሻን ከቆሻሻነቱ ባሻገር ለኛ የሚያዋሉ ነገር አለወይ?

**ወሰን :-** አው አሁን እያደረግን ያለነው ፌስታሉን ለብቻ አድርገን ኘሮሰስ እንዲሆን ከአንድ ፋብሪካ ጋር ተነጋግረን ነው:: በዚህ ጉዳይ ትዕይንተ ጉንደር በተባለው ኘሮግራም ላይ ከአሜሪካ ከመጡ ሰዎች ጋር ተወያይተናል:: ከዚያ በተጨማሪ የሙዝ ልጣጩ ፍጉን እንዲሁም ሌላውን በአንድ ላይ አርገን እርሻህ ላይ ብታደርገው እንዴት አይነት ማዳበሪያ ይሆናል መሰለህ ? አሁን በዚህ ጉዳይ ላይ ፋይናል ኘሮጀክቱ ላይ ተግሬውንም ትሬይን አርገን እንገፋበታለን::

**ራዕይ:-** ውበት ባቹ ፍልስፍና እንዴት ይገለፃል?

**ወሰን :-** ውበት አንደኛ እንደተመለከቱ ነው ሁለተኛ ነገር የመልክ ውበትን ብቻ ሳይሆን የውስጥ ውበትም ጭምር ነው ማድነቅ የምፈልገው የውስጥ ውበትንም ያየሁት በስሺ የተነሳ ለሥራው ያለው ፍቅር እጅግ ይማርከኛል:: የሠውን ልጅ መልኩ ያስጠላል ወይም ያምራል ብለህ መራቅና መቅረብ ተገቢ አይደለም:: ቆንጆዋ ጋር ሄደህ አስጠሊታ ነገር ልታገኝ ትችላለህ አስጠሊታዋ ጋር ሄደህ ደሞ ቆንጆ ነገር ልታገኝ ትችላለህ እና እግዚአብሄር ደሞ በአምሣሉ የፈጠረው ሠው አስጠሊታና ቆንጆ ተብሎ መከፈል የለበትም::

**ራዕይ:-** አሁን በጋሽ አበራ ውስጣዊ ውበት ከውጫዊዩ በልጧል ነው የምትይኝ?

**ወሰን :-** ሁለነገሩ ውብ ነው :: እግዚአብሄር ከእሱ ጋር ያገናኘኝ ሕይወቱን ሊጠብቅልኝ ሲፈልግ ነው ማለት እችላለሁ እንደሚታወቀው የኢትዮጵያ ህዝብ ሁሉም ሐብታም አይደለም እሱ ለጉዳና ተዳዳሪው ሁሉ ያለችውን ሣንቲም ሲሰጥ እኔስ? የሚል ጥያቄ በጭንቅላቴ ላይ ያታጭልብኛል:: ጥሩ መሆን ለራስህ ነው እና ለወጣቶቹ የሥራ ዕድል ብትፈጥርላቸው ታሥረው የተቀመጡትን ወጣቶች ሁሉ ታዓምር መፍጠሮ መፍጠር ይችላሉ:: እና ውጫዊዩም ውበቱን ልነግርህ አልችልም በጣም ልዩ እና ውብ ነው::

**ራዕይ:-** እኛ ኢትዮጵያውያን ከጀግንነታችን ባሻገር በውበታችንም የብዙዎችን ቀልብ ለመሳብ ችለናል:: ለመሆኑ ይህ በእንዲህ እንዳለ የአካባቢያችን ውበት ምን ይመስላል?

**ወሰን :-** እሱ ነው የሚያሳፍረን እኛ ኢትዮጵያውያን አካቢንጅናችን ከአድማስ እስከ አድማስ ናኝቷል:: ፈረንጆች እኮ እኛን ነው የትዳር አጋራቸው ለማድረግ የሚሮጡት ግን

ወደ ገጽ 21 ዞሯል

« አንገብጋቢው ጉዳይ ለወጣቱ የስራ እድል መፍጠር ነው::»

# ትኩረት

በኤች አይቪ ኤድስ ላይ የሚያተኩሩ ጽሁፎች በዚህ አምድ ስር ይስተናገዳሉ

በሳምሶን አብደላ

አንድ እውነተኛ ታሪክ ልንገራችሁ:: ነገሩየተፈፀመው ከአዲስ አበባ ትንሽ ራቅ ብላ በምትገኝ አንዲት የገጠራማ መንደር ወስጥ ነው:: ልጅት ከጉረቤት ሰው ይሞትና እዚያ ለማምሸት ትሄዳለች:: ወጣት እንደመሆኗ ከወጣቶች ጋር ተቀላቅላ በሚያስቀው እየሳቀች በሚያሳዝነው እያዘነች ጨዋታ ጨዋታን እየወለደ ይሄድና በድንኳኑ ካሉት አምስት ወንዶች ጋር መግባባት ትጀምራለች:: ወንዶቹ ትንሽ ቆየት አሉና ተከታትለው ወጡ:: አንዳች የልጠረጠረችው ልጃገረድም አገር ሰላም ነው ብላ ወደ ቤቷ ለመሄድ ትነሳለች:: ከመንገዱ ጨለማ ጋር እየታገለች ግራ ቀኝ እየተወላከፈች መንገዷን ስትጀምር ከየት መጡ ያላለቻቸው እጆች እጆቿን ይይዛሉ:: ለመታገል ብትሞክርም የወንዶቹ ጉልበት ከጉልበቷ በላይ ሆነና በዚያ እማኝ በሌለው ጉራንጉር ውስጥ ተረባርበው ገላዋን ተቀራመቱት:: መቼም አበሻና ወሬ ለዘመናት ሲዋደዱ የኖሩ

ጓደኛሞች ናቸውና በማግስቱ የልጅቷ መደፈር በሰፈው ይወራል:: «ጆሮ ለባለቤቱ ባዳ ነው» እንዲሉ ነገርየው ቤተሰቦቿ ጋር አልደረሰም:: እሷም ለማንም አላወራችም - የሆድዋን በሆድዋ ይዛ ማምንታት ተቆጠሩ:: ታዲያ አንድ ቀን ትዳር ፈላጊ ይመጣና በሐገር ወግ መሰረት ሽማግሌ ይልካል:: ሰውየው ጥሩ ደመወዝ አለው:: የልጅት ቤተሰብ ስለ ኤች አይቪ የጠለቀ ግንዛቤ ባይኖራቸውም ሰውየው እልፎ አልፎ በጣም ያመው ስለነበረ የምርመራ ወረቀት ይጠይቃሉ:: ሌላ ቀጠሮ ተያዘና ተለያዩ:: በሁለተኛው ቀጠሮ የተላኩት ሰዎች ነፃ የምርመራ ውጤት ይዘው ተመለሱ:: በሶስተኛው ጊዜ ሰርግ ይደገስ ተባለ:: አሁን ግን ባል አንድ ነገር ሰማና ልጅቷን አጥብቆ ጠየቃት « እውነት ነው ነገሩ? » ልጅት እውነቱል ለመናገር ድፍረት አጣች:: እናትና አባት ልጃቸው በድንግልና እንደምትኖር ያውቃሉ:: ከወጣቱ ወገን የተላኩት ሰዎች መለስ ብለው ልጃችሁ ልጃገረድ ናት? የሚለውን ጥያቄ ያነሳሉ::

ብዙ ሲከራከሩ ከቆዩ በኋላ ቤተሰብ ልጃቸውን አጥብቀው ጠየቋት:: ልጅተ እውነታውን ሽምጥጥ አድርጋ ካደች:: ሰርግ ደረሰ . . . አሁን ሙሽረት

ተሞሽራለች:: « እረ ኩሉን ማን ኳለሽ» ሲዘፈን: ሰርገኛው ትከሻውን ለመፈተን ሽርጉድ ሲል አባት በድንገት ተነሱና የምርመራውን ወረቀት በድጋሚ ጠየቁ:: መጠየቃቸው ባልከፋ: የሚገርመው ግን ሙሽራውም ሙሽሪትም አብረው ይመርመሩ የሚል ሃሳብ አለማንሳታቸው ነው:: . . . የሳቸው ልጅ ዓዲቅ ናታ! የሳቸው ልጅ ጨዋ ናታ! እንደምንም ዝግጅቱ አለቀና ሰውየውም የምርመራ ወረቀቱን በድጋሚ አሳይቶ ሙሽሪትን ይዞ ወደ ቤቱ:: . . . አሁን ጫጉላ ቤት ናቸው:: ቢታይ ቢታይ ምንም የለ . . . መቼም የዘንድሮ ድንግልና ጥሉ ሲሄድ አይታወቅም:: ባለ አንጀቱ ተቃጠለ:: የሚይዝ የሚጨብጠው ጠፋ:: በተለይ የልጅቷ ውሸት ንዴቱን አባባሰው ከዚያም ልጅቷን በደንብ ከደበደባት በኋላ መልሶ ወደ ቤቷ ይልካታል:: ልጅት በጣም በሚያሳዝን ሁኔታ

እምርጥ በመንቀቱ የስነ ልቦና ችግር ገጠማትና ለሶስት አመታት ያህል ከቤት ሳትወጣ ተደብቃ ቆየች:: በኋላም ተረጋግታ ወጣ ስትል የሚወት ሰጣ ፋንታ አትጣሚው ብዙ ነውና ከአንዱ ጋር ደም ተገኝታ አብራ መኖር ጀመረች:: በመሐል እርግዝና መጣ:: አሁንም ልጅቷ እርግዝናዋን ደብቃለች::የሆነ ሆኖ የመውለጃዋ ጊዜ ይደርስና ትታመማለች:: አሁንም ቤተሰብ ነገሩ አላወቀም:: ሐኪም ቤት ሲወስዱዋት ሐኪሙ « አሁን ትወልዳለች» ብሉ ሲነግራቸው የማያውቁትን ነገር በመስማታቸው ድንግርግራቸው ይወጣል:: ልጅት በመንደር ዛኪም እርዳታ ልትወልድ ብትችልም ሐኪሙ የእንግዴውን ልጅ አወጣለሁ ሲል ሳያውቅ ለላ ስህተት ይሰራና ይህችው ያልታደለች ሴት በጣም ብዙ ደም ፈሰሳት:: ሐኪሙ ደነገጠ:: ነገሮች ሁሉ ከአቅም በላይ መሆን ሲጀምሩ ወደ ጥቁር አንበሳ ሆስፒታል መጓዙ ብቸኛ አማራጭ ሆነ:: ግና ቀድሞ ፊትዋን ያዞረችባት ሂወት በቀላሉ ባለመሻርዋ የልጅት ዕጣፋንታ ወደ ማትናት ሆነ:: የቀድሞ ባለቤትዋም ባለማወቅ በሰራው አፀፀስ: ለተመኘው ጣፋጭ የትዳር ሂወት ፋንታ ወደ መቃብር መውረዱን ግድ ሆነ::

እምዝ ይህንን የመሳሰሉ ቡዙ ሺህ አሳዛኝ ታሪኮችን ብናሳልፍም: የቤታችን ሰላም በተደጋጋሚ የሞት ጨኸቶች ቢደፈርስም: የምንወዳቸው ሰዎች በትንጣት ስህተት ካለጊዜአቸው ለዘላለም ቢያሸልቡም: አምን ዛሬም ድረስ ተኝተናል:: ልክ እኩለ ቀን ላይ እንደሚወስዱት ጣፋጭ እንቅልፍ ጭልጥ ያለ መኝታ ላይ ነን:: የሚናገር እንደበት እንጂ የሚያደምጥ ጆሮ የለንም:: ጤንነትን እየናፈቅን: ካለመናር ጋር ተዛምደን የእድሜ ገመዳችንን አሳጥረን ሞት ሞት በሚሸት ዘመን ላይ ብንገኝም ከተኛንበት ከመንቃት: ከወደቅንበት ለመነሳት ከመሞከር ይልቅ በዝምታችን ጨኸት ተሰለቻችተናል::

በእርግጥ ዝምታ መጥፎ አይደለም:: ዝምታ ወርቅ ነው ይባል የለ! በዚህች ሁካታ በበዛበት አለም ዝምታን የማይናፍቅ ማን አለ? አሳሳቢው ነገር ግን ዝምታችን የሰላም አለመሆኑ ነው:: አዎን ከዝምታው በስተጀርባ ትልቅ ጨኸት ይሰማል:: «ካለመናገር ደጅ አዝማችነት ይቀራል» እንዲሉ ዝምታን በመምረጣችን ምክንያት በኢድስ ላይ የደጅ አዝማችነት እንኳን ሹመት አተናል:: ደጅ አዝማቹም: ፊት አውራሪውም: ንጉሱም እሱ ከሆነ ይኸው ሁለት አስርት አመታት ተቆጠሩ:: ሁላችንም እንደሚገባን ዛሬ በጥቂቱም ቢሆን ስለ ኤድስ ያላወቀ የለም:: እንደውም አንድ ጓደኛዬ ይህን ነገር ሲገልፀው « ዘንድሮ ለአንሰሳቱ መናገር ብቻ ነው የቀረን » ነበር ያለው:: ችግሩ ያለው ታድያ የሰማነውን

በልቦናችን አሳድረን እውነተኛ የለውጥ ሃዋሪያት ለመሆን አለመነሳታችን ላይ ነው:: ሌላው ቢቀር እኩ እራስን ማዳንም ትልቅ ነገር ነው:: ሀ - ራስህን አድን አይደል ጨዋታውስ! ይህንንስ አስበንበት የምናደርግ ምን ያህሉቻችን ነን? መቼም ዘንድሮ ጥያቄ ጥያቄን እየወለደ ሁሉም ችግሮቻችን መልስ አጥተው ቀሩ እንጂ ብዙ መጠየየቅ ብንችል በወደድን ነበር:: ለዘመኑ ትውልድ እራስ ምታት የሆነ ትልቅ የጥያቄ ምልክት በሁላችንም ልብ ውስጥ በጥቁር መሐተም ታትሞ ይገኛል:: በአንድ ወቅት« ሁላችንም ጊዜአችንን የምንጠብቅ ሙታኖች ነን::» የሚል አነጋገር መስማቴ ትዝ ይለኛል:: ታዲያ የሰው ልጅ ሁሉ መሞት ዕውን ከሆነ የመሞቻ ጊዜአችንን መጠበቁ ላይ ትግስቱን ያጣነው ለምን ይሆን ?

«አሳሳቢው ነገር ግን ዝምታችን የሰላም አለመሆኑ ነው::
ከዝምታው ጀርባ ትልቅ ጨኸት ይሰማል:: »

በቀድሞ ጊዜ የሰው ልጅ ከሞት ለማምለጥ ታላቅ ትግል ያደርግ ነበር:: ሞት ወደ ሰው ሲመጣ፡ ሰው ከሞት ለማምለጥ ሲጥር የእድሜና ታዳኝነት ፍልሚያው ለሚመለከተው

ሰው እራሱ አንጊ ነበር:: ዛሬ ዛሬ ደሞ ታላቁ ሼክስፒር « ከጊዜና ከማህፀን እያደር ጉድ ይወለዳል » እንዳለው ካለንበት ዘመን ጉድ ተወለደና የሰው ልጅ በተራው ሞትን ማሳደድ ጀምሮ የራሳችንን ጉድጓድ እራሳችን መቆፈር ያዝን::

ለወትሮው «የኤሌክትሪክ ጠባሳ ያየ በእሳት አይጫወትም » የሚሉት ብሂል የእኛው የኢትዮጵያውያን ነበር:: ግና ከሃገርኛ የስነ ፁሁፍ ቅርስነቱ ባሻገር ወደ ህሊናችን ሠርጾ አንዳች ፋይዳ ሲያመጣ አልቻለምና ይኸው በጠባሳ ላይ ጠባሳ እየጨመርን አካላዊና መንፈሳዊ ድካማችንን በይሁንታ ተቀብለናል:: የሆነ ሆኖ ዛሬ መወቃቀሱ መፍትሄ አይሆነንም:: አንድ ነገር ብቻ እናስብ፡ አዎ መኖር አለብን:: የሂወትን ጥኡም ዜማ ሙክ እያልን ማዜም ይገባናል:: Let's fight sleep together አይደል የዘመኑስ ቋንቋ! በቃ ከተኛንበት እንነሳ::

## አጎቴ

ለሰሰለ ባለው የክላክለ ቃናቸው
ዞር ብዬ እንዳየሁዋቸው
ሲጣራ አባባ
አቤት የመኪናቸውድምጽ
ሆድ ሲያባባ
ጥሪቸው ሲደጋገምብኝ
ዞር ብዬ እንዳየሁዋቸው
ለከለ የትላንትናው ሰውዬ
ባለውለታዬ ናቸው
ከትምህርት ቤት ስመለስ
ከሚጥለው ዝናብ ለመጠለል
ወዲያ ወዲህ ሳቅማማ
በርህሩህ ልቦና እንደበታቸው
ያስጠለሉኝ ሰውዬ ባለውለታየ ናቸው
ዛሬማ ቢደጋገምብኝ ጥሪያቸው
ዞር ብየ እንዳየሁዋቸው
አልሞከርኩም ልሸሻቸው
ጭራህ ሄድኩ ልጠጋቸው
ትዝ ብሉንኝ ውደታቸው
ገባሁ ተከፍቶለኝ መኪናቸው
አባባማ ብልጥ ናቸው
የዘመኑ ስልጣኔ የገባቸው
ሃይ ነበረ መልሳቸው
ወጣት ይዘው ምን ገዶአቸው
አባባ እኮ ሙድ አሳቸው
ገሰገሱ ፈረጠጡ
የዘመኑን መቅሰፍት ስያመጡ
በቀኝ ዕጃቸው ግራ እጄን
ብሉም ጭኔን እያሻሹ
«ዘናብለሽተቀመጭ»
ምነው ፈራሽአሉንኝ
በቀኝ ጃቻቸው ጭኔን እየጨበጡ
ጨዋታ ብጤ ሲያመጡ ሞከሩ
መጀመሪያ ስማቸውን ተናገሩ
ደንገጥ ብዬ«ማን»አልኩቸው
ያልሰማሁ መስሉቸው
እጆችን ጭኖችን አሻሽተው በእጃቸው
ግና ወደ ሴላው መች አሳለፍኩዋቸው
ዘመን ጋር ተራምደው አጎቴ ሰልጥነው
ይሄውና አረፉት ሹገር ዳዲ ሆነው::

ሜሮን አበበ
(*Harar S.S.School*)

ኢብሮሰን

ለማንኛውም ነገር መግቢያው ሰላምታ ነው ይላለ የተማሩ ሰዎች ::እናም ሰላም ለናንተ ይሁን በማለት ወደ ዋናው ጽሁፌ ልመለስ::አሃ!ልክ ነዋ የሰላምታ ጋጋታና ብዛት ምን ይፈይዳል? ከከፌ ይነጥለኝ ! የዘመኑ ሰላምታ ፈሩን የለቀቀ ይመስለኛል::

ውይ በአሜሪከኖች እንዳዱማ ስልችት ያደርጋች-ሁዋል::ጀ!ሰላም ነህ ?ጨንራ-ሀ ይፈጫል?..ደምህ ይዞራል? ?በቃ አስልቺ ሰላምታ የምር ግን ቆም ብየ ሁኔታ ስራቸውን ሳስተውለው የክሊኒከችን የህክምና ባለሙያወች ትዝ ይሉኛል::በቃ እነሱም እንደዚሁ ናቸው::ነገርን ነገር ያነሳዋልና ስለነሱም ትንሽ ለ ማለት ወደድኩ::እኔ መቸም ቢያመኝም ቢፈልጠኝም ክሊኒክ በፍጹም አልሄድም ::ምክኒያቱም ትርፉ ጊዜ መግደል ብቻ ነውና !በዚያ ላይ የጥበቃ ሰራተኛው 20 ሰው ከሞላ ከዚያ በላይ አይደለም ቀላል ደም ቢፈስ እንኳዋን ድርሽ አያስደርግም ሃገር ቢሄድ እኮ ጾሙን ውሎ ጾሙን ያድራል::አሃ! ልክ ነዋ በአሜሪን በተሰፋይቱ ምድር ቀልድ የለም ::ሃሜትና ወሬ ከስም የዘለለ ትርጓሜ የላቸውምና::እንዳውም አሜሪ-ከኖች ለጊዜ ያላቸውን አጽን-ኦት በዚች አባባል ቁልጭ አድርገው አስቀምጠውታል::

<We are never to slave ,but the clock>እኛ ከጊዜ በስተቀር የማንም ባሮች አይደለንም ይላሉ ታዲያ የኛ ሰው እንዴት ብሎ ነው አሜ-ሪከንን የሚመኘው ?

ታዲ ያ የኛ ሰው በምን ትጋቱ ነው ዋሺንግተን ዲሲን የሚመኘው ?አሚሪከ ውስጥ እያንዳንዷ ሰከንድ በገንዘብ እስንልተመነዘረች ድረስ አይደለም መኖር ውሎ ማደር ምን ያህል ከባድ እንደ-ሆነ ለመገመት አያዳግትም ጀለሰ እኛም ሀገር ኑሮ እየተወደደ መምጣቱን አስተ-ውለህ ታውቃለህ? ልብስ ውድ ..ጫማ ውድ. .ጡት ማስያገዋ ውድ. .የምር ኩኩ ሰብሰቤ ትንሽ ጊዜ ሲጠኝ እያለችልህ ነው :: እዚህ ላይ ግን ኩኩ በጣም ተሳስተሻል ..ደግሞ ለሞላ ጊዜ ትንሽ ማለትን ምን አመጣው?ወይኔ እኔን ጠይቀሽኝ ቢሆን ኖሮ በርከት ከት አድርጌ እለቅብሽ ነበር::ኩኩ ይሄን ጥያቄ ግን ለአንድ:: አሜሪከዊ ብታቀርቢው «ሀርድ» ውስጥ ነሽ::

በርከታ ሰዎች በየቤታቸው ግድግዳ ላይ አሊያም በጭንቅላታቸው «ሃርድ ዲስክ » ውስጥ «ከልተሳፈሩበት ሮጦ ተሽቀዳድሞ ጊዜ ታክሲ አይደለም አይጠብቅም ቆሞ»የምትለዋን የድሮ ግን ግን በጣም በሳል ጥቅስ «ሎድ»አድርገዋታል::ይሁን እንጂ ያሁኑ ትውልድ ለዚህ አባባል ብዙም ደንታ ያለው አይመስልም:: በቃ የጊዜ ሃብታም ነዋ..ጊዜ ወደ ፊት በ200 M/S (በፊዚክሰኛ)

**«መአት ዶክተሮች በርከታ ፕሮፌሰሮችንና መሀንዲሶችን ይዘን እንለምናለን እንራባለን ለምን ? በእርግጥም ይሄን ጥያቄ ለመመለስ ሞራሉም አቅሙም ብቃቱም ያለው ዜጋ ይቺን ሀገር ያለጥርጥር ይለውጣታል::»**

ከዚህ ሁሉ ታዲያ «ታሞ ከመማቀቅ አስቀድሞ መጠንቀቅ»ነውና በሰላም እራሳችንን ጠብቀን መኖርን የመሰለ ነገር የለም:: ቅድም ስለምን ነበር አያወራሁ የነበርኩት?አዎ!ሲለዘመኑ ሰላምታ ቅጥ ስላጣው ሰላም ስለሚነሳው ሰላምታ ..ጸረ-ጊዜ ሳቅ አይሉት ጨዋታ ስለሆነው ሰላምታ ነበር::ቆይ ግን አንድ ሰው ሰላም ብቻ ብሎ ማለፍ አይችልም እንዴ?ከሳሀ..ጠቆርክ ወዘተ ምን አመጣቸው?

ለመሆኑ ሌላ የሚወራ ጠፉ እንዴ?እኔ በበኩሌ እስከ ማውቀው ድረስ ኢትዮጵያ ውስጥ ከፍተኛ የወሬ ሪሶርስ እንዳለን ነው::ግን ምን ዋጋ አለው ተሜ .. የውጭ ኢንቨስተሮችን ገና ከሩቅ የሚያባርር ደህነትን የሚጣራ ..ተንኮልንና ሃሜትን የሚያበ-ረታታ ..አ!አ!ይሄ «ሪሶርስ » ሳይሆን (waste) ነው:: አሁን እዚህ ቁጭ ብየ ሳስበው ግርም ይለኛል :: ምንድነው እሱ አትሉኝም? የኛ ሰው አሜሪከን ሃገር ከጡቱ ይልቅ ማስያዣው የተወደጀበት ውድ ዘመን ላይ ደረስን::ርከሹ ነገር ወሬ ብቻ ነው::ዶርም ውስጥ ይወራል.. ከፌም ይወራል ..ላይብረሪም ይወራል ..እንዲሁም መምህሩ እያስተማሩ ጎንለጎን ይወራል ወሬ ተኮር ስትራተጂስት ሆነን አረፍነውኮ!

መቼም ከወሬ ብዛት የተነሳ የአንደበታችን ጡንቻዎች ምን ያህል ጠንከራ እንዲሆኑ ይታየኛል:: ሌላው እኛ ሃገር ርከሹ ወሬ ነው::ጊዜ ተርፎን ይሁን አጠቃቀሙን ሳናውቅበት አይ-ገባኝም የጊዜ ሃብታም ያልሆነ የለም ::ምን እንዴት አለው ?የሚያምታታም ሃሳብ አይደለም ..ይህን እውነታከ አርቲስቶቹ አምነውበት ዘፈናቸው ተደማጭነት ያገኘነው የገነኑ ድምጻውያን ለዚህ ሃቅ ምስክርነታቸውን እየሰጡ ይገኛሉ ::አሃ! ምን ግራ ያጋባሀል ሙዚቃ አዳምጨ አላውቅም ከአላልከኝ በስተቀር አሁን ይሄን ሃቅ ከአንተ ይሰወራል ?ሩቅ አትሂድ እዚሁ እፊትህ ሲፈተለክ ትውልዱ በ2000Km/hr ወደ ኋላ ይሮጣል..መሮጥ ከተባለ::ዛሬ ታክሲውንኩዋ ቆሞ በማይጠብቅበት ዘመን የኛ የ-ጊዜ ሃብታም መሆን ያስገርማል::

ታዲያ የጊዜ ሃብታም የወሬ ቱጃር የነገር መሃንዲስ ይዘን እንዴት ማደግ እንችላለን?አንድ በጣም የሚያስገርመኝ ና ረፍት የሚነሳኝ ጥያቄ አለኝ::ምንድነው አትሉኝም ? ድሮ ተክኖሎጂ ስሙእንኩዋን በማይታወቅበት ጊዜ ኢትዮጵ-ያ በስልጣኔ ቀደምት ነበረች ዛሬ ግን በተቃራኒው መአት ዶክተሮችን በርከታ ፕሮፌሰሮችንና መሃንዲሶችን በጉያች-ን ይዘን እንለምናለን..እንራባለን..ለምን በእርግጥም ይሄን ጥያቄ ለመመለስ ሞራሉም አቅሙም ብቃቱምያለው ዜጋ ከለ ያለጥርጥር ይችን ሀገር ይለውጣታል የሚል አመለከከት አለኝ:: ደህና ሰንብቱልኝ::

# ፀ ፀ ት

በሳምሶን አብደላ

እግዚአብሔር ነፍሱን ይማረውና አባቴ የሆነ ጀዝባ ነገር ነበር:: ስነገሩ እናቴም ከሱ አትሻልም:: እንደነገረችኝ ከሆነ ለለጅነቷ እግጅ በጣም ቀልቃላ ነበረች:: በተለይ ማታ ማታ ከእኔና ከሁለት ወንድሞቼ ጋር ተቀምጣ ብዙ ብዙ 'ለልጅ የማይነገሩ' ነገሮችን ትነግረን ነበር በትምህርት ቤቷ የነበራትን ቀልቃላነት፣ቤተሰቧን ከማስቸገሯ የተነሳ በውስት አክስቷ ጋር እንድትኖር መደረጉ፣ አክስቷ ጋር መኖሯ ደግሞ መረን አደግ እንድትሆንና ብዙ ወንዶችን ገና በልጅነቷ እንድታውቅ መሆኗን ሁሉ ዘርዝራ ትነግረን ነበር:: አይ እናቴ የዋህ ነበረች እኮ! የተለያዩ አጋጣሚዎች ከአገናኟት ወንዶች ጋር እንደሷ አባባል ስትጫወትባቸው - በእምብርክክ ስታስኬዳቸው ከርማለች:: የወጣትነት ላይፏንም እንደገጉድ ቀጭታለች:: ታደያ ያልታደለወ አባቴ በእምብርክክ ከመጡት አንዱ ነበር /በቁጥር ስንተኛ ው እንደሆነ ግን አልነገረችኝም::/

እግዚአብሔር ይመስገን እሱ በእምብርክክ እንደመጡት በእምብርክክ አልተመለሰም:: በለስ ቀናውና እናቴን እጁ ላይ ጣለለት:: በወጣትነት ፍቅርን ሲያጣጥሙ የአዲስ አበባን አውራ ጎዳናዎች እጅ ለእጅ ተያይዘው ሲያቆራርጡ ቲያትር ቤቶችን፣ ሲኒማዎችን፣ የዳንስ ምሽቶችን ሲያካልሉ ቆዩና በመጨረሻ ተዳር መሰረቱ::

ይህንን ሁለ ስታጫወተን ቆይታ ትናንሽ ወንድሞቼ በተቀመጡበት እንቀልፍ ጣል ሲያደርጋቸው እኔ ግን የሆንኩ ፈጣጣ ቢጤ ነበርኩ:: ታዲያ የመጀመሪያ ልጇ እንደመሆኔ ትልልቅ ሚስጥሮችን የምታወራልኝ ለኔ ብቻ

ነበረ:: ስለሴት ጓደኞቿ፣ ስለ ልጅነቷ፣ ስለ ... እያወራን እንደቀልድ የአባቴ መምጫ ሰዓት ይደርሳል:: ከሌሊቱ 9:00 ሰዓት:: የወጭው የቆርቆሮ በራችን በአባቴ ተደጋጋሚ ቡጢዎች ቋቋታው ሲያንቀረቁረው እናቴ ማንነው ብላ ትጠይቃለች:: መጠየቋ ለአመለ ያህል እንጂ የመጣው አባቴ መሆኑን የምናውቀው ገና የወጭው በር ስልቱን ባልጠበቀ አመታት ቋቋታውን ሲያሰማን ነው:: "እኔ ነኛ እ... ኔ" ኩልትፍትፍ ያለ አስቀያሚ የሰካራም ድምጽ በስርቅታ እየታነቀ ይመልሳል:: "ከፈቺ" ቋ-ቋ-ቋ ...እናቴ ዛሬስ ብሶበታል ብላ ከአልጋ ትነሳለች:: የአባቴ መጠጣትና ሰዓቱን ጠብቆ መምጣት የተለመደ ቢሆንም

ለእናቴ ግን ሁለም አዲስ ይሆንባታል:: 'ዛሬስ ብሶበታል' ትላለች ሁልጌዜ ::በውስጥ ልብሷ እንዳለች ከአልጋው ወታ ነጠላ ጫማውን ታደርግና በሩን ለመክፈት ስትሄድ ዳሌዋ ከአይኔ ያርፍና ነጩ የውስጥ ሱሬዋ ቅርጽ ወለል ብሎ ሲታየኝ ለአፍታ እናትነቷ ይዘነጋኝና ምራቄን ደጋግሜ እውጣለሁ:: እግዜሔር ይቅር ይበለኝ የተረገምኩ ልጅ!- በበሩ በኩል አልፎ እየተወላገደ የሚገባው አባቴ በስካር መንፈስ ቀረርቶውን፣ ዘራፋን፣ ሽለላውን እንደጉድ ያስነካዋል:: "እኔ እኮ" ይላል አባቴ " ዛሬ ቀን ጎ- ደለለ ብኝ እንጂ- ጂ- ይሄኔ-የት ... ደርሼ ነበ-" ከአልኮለ አስቀያማ ጠረን ጋር አብረው የሚፈሱት ተደጋጋሚና አሰልቺ ቃላቶች መቋጫቸው ስርቅታ ብቻ ነው::

እናቴ በሩን ዘጋግታ ትመጣና አባቴን ለአመለ ያህል ደገፍ አድርጋ ወደ ጓዳ ታስገባዋለች:: ይሄኔ እኔ ብርድልብሴን ተሸፍኜ በትንሹ ብቻ ገለጥ አደርገውና ቀስ ብዬ የአባቴንና የእናቴን ትርኢት በጉጉት እመለከታለሁ::

ሁልጊዜም ጉጉቴ በጨመረ መጠን ታዲያ የግራ እጄ ጣቶች ወደ ታች ወርደው ወንድነቴን እንቅ አድርገው ይይዙታል:: የት አባቱ!

ጩኸቱ ያሰለቻት እናቴ ባለቤቷን በግርምት እያየች " በሌሊት እንዲህ የሚያስጮህ ምን ልክፍት ነው ባካችሁ እኔስ መዌም ፈርዶብኛል አንጄ ጎረቤቱን ግን እንቅልፍ የምትነሳው ምን አድርጎህ ነው?"

"ዝም- በይ" የአባቴ ጩኸት ያቋርጣታል:: " ገረ-ቤቤት-ምን አባ-ቱ አገባው በገንዘቤቤ ነወ እኮ የጠጣሁት የምጨኸውም በ-በቤ ቴ ነው"

" እሺ በቃ ተኛ አሁን ::" እናቴ ድምጿን ለሰለስ አድርጋ በመማፀን አይን እያየች ትጠይቀዋለች:: የመተኛት ነገር ሲነሳበት አይኑ ይበራና አባቴ የእናቴን ውበት መቸከል ይጀምራል::

" ተኛ እኮ ነው የምልህ" እናቴ ደግማ ትጠይቀዋለች::

" አንቺ ደግሞ ይሄንን ው-ውስጥ ልብስ መቼ -ቼ ገዛሽው... አቤት ..." ፊቱ የቅቤ ቅል መስሎ ወደሷ ይጠጋና ትከሻዋን ማሻሸት ይጀምራል::

ይሄኔ እኔ ባለሁበት መቁነጥነጥ:: የግራ እጄ ጣቶች የያዙትን አለቀቁም::

"ተው እንጂ" ለወጉ የእምቢታ ቃላትን ጣል ታደርጋለች እናቴ::

" እስቲ አ-ውልቂው" አባቴ ውስጥልብሱ እስኪወልቅ መቸኮሉን ስለምታውቅ ነው መሰለኝ እናቴ ድርቅ ትላለች::

"አንቺ"

" ምንድነው ?"

"ባለ-ቤትሽ ነኝ እኮ" ወንድነቱ ደርሶ ይተናነቀውና የሸሚዙን እጆች ወደ ላይ ይሰበስባል::

" እምቢ ካል-ሽ ደ-ደግሞ " እጁን ወደ እግሮቿ ሰዶ ልብሷን ሊሰበስብ ሲል እናቴ ትቆጣለች:: የውሸት ቁጣ፤ የማጓጓት ቁጣ::

" ረጋ በል ምስትህ እንጂ ገረድህ አይደለሁም:: ለዛ በስ:: " ይሄንን ተናግራ በቁማ ረጅሙ የውስጥ ልብሷን ወደ ታች ቁልቁል ስትለቀው እኔ ትንሿ ልቤ ድ-ው-ድ-ው እያለች በአፌ አፈትልካ ልትወጣ ትደርሳለች:: የአባቴ ነገርማ አይነገርም:: በዚህ ሁኔታ አባቴ የእናቴን ፈቃድ ያገኝና አለም ዘጠኝ ትሆናለች:: እናቴ ከየት እንደመጣ አትጠይቀውም::

እሱም አይናገርም:: ብቻ ተያይዘው የእውር ድንብራቸውን ከአልጋ መውደቅ ይቀናቸዋል:: አባቴ ከሞተ አመታት ቢቆጠሩም እናቴ ባል አላገባችም ብቻ አንዳንድ ቀናት ተኳኩላ እየወጣች አምሽታ መመለሱን ተያያዘችው:: ሁኔታዋ ግራ ሲገባኝ ፈራ ተባ እያልኩ "ወዴት ነሽ ? " እላት ነበር::

" ምን አገባህ ልጄ እንጂ አይደለህም " የሚሉ ጠረኛ ቃላቶቿ ደሮዬንም ልቤንም ሲወጉት ዝምታ ነበር መልሴ :: አንድ ቀን ምን ሆነ መሰላችሁ አንዲት አጭር ቀይ ሴት እኛ ቤት ትመጣና ቡና ተፈልቶ እየጠጣች ከእናቴ ጋር ሲያወሩ ቆይተው ሴትየዋ ድንገት ሳት ይላትና

"አዳዲሶቹ ባሎችሽ እንዴት ናቸው እኔ ግን ያንን አረጅሙን ብትይዢው ጥሩ ይመስለኛል:: ኢንጅነር ነው አሉ ደህና አድርገሽ ትግጭዋለሽ :: " ስትል ትናገራለች::

እናቴ የምትይዝ የምትጨብጠው ጠፍቷት በሃፍረት ተሽማቀቀችና ከቡና ማስቀመጫ ላይ 50 ሳንቲም አንስታ ሂድ ስኳር ገዝተህ ና ብላ ላከችኝ:: ውጣ ማለቷ እንደሆነ ገብቶኛ ል:: ተመልሼ ስመጣ ጨዋታቸው መልኩን ቀይሮ ጠበቀኝ:: እንግዳዋ የእናቴ ጓደኛም ተነስታ ሄደች::

አንድ ሐሙስ ምሽት እናቴ እንደተለመደው ተኳኩላ የቁምሳጥናችን ረጅሙ መስታወት ፊት ቆማ እራሷን መመለከት ያዘች::

" ደግሞ ከመሸ የት ልትሄጂ ነው?" ስል ጠየኳት::

" ለቅሶ አለብኝ አንድ ጓደኞችን አክስቷ ሞተው መርዶ ተቀምጣለች"

" ድሮ ለቅሶ ቤት ስትሄጂ ነጠላ ለብሰሽ ነበር:: ዛሬ ... "

"ዝጋ " ጩኸቷ ጆሮዬ ላይ አንባረቀችብኝ::

"ልጄ እንጂ ባሌ አይደለህም:: የትም ልሂድ:: ወይ ጉድ! ልጅ ከበላ ከጠጣ ምን ይጎድለዋል? ምግብህን ይዤአልሄድ:: አንተ እኮ ከተበላሽህ ቆይተሃል::" ሽንፈቷን በቁጣ ሸፋፈነችው::

ጥቁር ቦርሳዋን ከጠረጴዛ ላይ አንስታ ስትወጣ ለሠራተኛ ችን የሆነ ነገር ሹክ አለቻት::

ቀናት እየተዋለዱ ህይወት ገዞዋን ወደ ፊት ስትቀጥል እናቴ አንድ ቀን ጤነኛ ..አንድ ቀን ታማሚ መሆን ጀመረች:: ይባስ ብሎ ህመሙ ፅናባትና ባልለየለት በሽታ ከአል ጋር ዘመድ ሆነች:: የመጀመሪያ ልጇ ስለሆንኩኝ ምስጥሯን - ችግሯን- ጭንቀቷን ሁሉ ታዋየኛለች:: ታዲያ አንድ ቀን ለብቻዬ ጠራችኝና ዛሬም ድረስ ከጆሮዬ የሚያቃጭሉ አስቀያሚ መርዶ የያዙ ስድስት ፊደላት በለሆሳስ ሹክ አለችኝ " ፖዘቲቭ ነኝ::" አላለቀስኩም፤ አልተናደድኩምም ብቻ የሆነ ባዶነት ከውስጤ ሰፈረ:: ልቤ ድንጋየ የሆነ መሰለኝ:: ከእናቴ ጋር በረጅም ዝምታ ተውጠን ከቆየን በኋላ በቀስታ እየተራመድኩ ክፍሉን ለቅቄ ወጣሁ::

ህመሟ እየበረታ ሰውነቷ እየከዳት ሲሄድ የ10 ዓመት ህፃን ልጅ አክላ በትልቁ አልጋ ውስጥ ተኝታ ሳያት አይኖቼ በእምባ ተሞሉ:: ነጫጭ አይኖቿ ደፍርሰው ሰውን ማየት የፈሩ ይቋስል

ከጉድጓዳቸው ስር ተደብቀዋል:: አቤት ማሳዘኗ! የጉንጮቿ አጥንቶች ገጠው - ፊቷ ንጥቆና ፀጉሯ ለማህላ ያህል ከጭንቅላቷ ላይ ቀርቶ እናቴ እንደተነፈሰ ፊኛ ኩምሽሽ ብላ ሳያት ሲቃ ተናነቀኝ:: ልታናግረኝያሰበችው ነገር ያለ ቢመስልም የደረቁት ከንፈሮቿን ማላቀቅ ተስኗት አይኖቿን አይኔ ላይ ተክላ...

ዛሬ የዩኒቨርሲቲ ተማሪና ገና ወጣት ልጅ ብሆንም ጥላውን ያጠላብኝ ሃዘን ግን ጨርሶ ከአጠገቤ አልራቀም:: እናቴን፣አባቴን መናፈቅ የዘወትር ሥራዬ ቢሆንም አነስ ዘላለማዊ ሽልብታን አሸልበዋል የሚለው እውነታ ግን ውስጤ አሜን ብሎ አልተቀበለም:: እስቲ የእናተን መሞት ማን ያምናል? ... ያውም በኤ

... እንጃ! ግን ቆይ በማነው የሚፈረደው? ጥፋቱስ የማነው? የፈጣሪ? የእናትና የአባቴ? ወይስ የዘመኑ?

ሴቶችን ብወድም የፍቀር ነገር ግን አልዋጥልህ ይለኛል:: በተለይ የጭለማ ወከ የሚሉትን ነገር እጅግ እጠላዋለሁ:: በቃ አንዳች ነገር ወደ ሞት የሚወስደኝ ይመስለኛል:: እና ልቤ ምሐዘን እየደማ- እየኔ እምባን እያዘነበ... በውስጤ ባደነት ነግሶ... ባልሰራሁት ሃጢያት የሀሲና ወቀሳን እትርፌአለሁ:: ዘላለማዊ ፀፀት ጭንቅላቴን በጥቁር መጋረጃ ጋርዶት ይኸው ዛሬም ድረስ እኖራለሁ:: ዳሩስ ...

ይታደሉታል እንጂ አይታገሉትም አይደል አባባሉ ?" ... አለመታደልን መታደል... ይሁና!

ተፈፀመ

## አይናፋር ወኔ

አይናፋር ነኝ ዕኔ
ነይልኝ ከጎኔ
ልሳለምሽባይኔ
መቸም የለኝወኔ::

ምንክሰው ግርማ

---

## ረመጥ

ንፁህ አየለ

ረመጡ ... ረምጦ፣
እሳቱ ... አፍጥጦ፣
ህይወት ...ቅጡ ጠፍቶ፣
መከራ ... ሰርፍቶ፣
ማለፍ እንዳልቻለ፣
ላይችል እንዳስቻለ፣
ላይሰጥ ...ሰጥቶ ባናት፣
የመከራን ጥቅት፣
በእምነት እዳ ግቶ፣
ሀሲና መላ አጥቶ፣
ስርቆሹ አራምጦት፣
ረመጡ አፋጂቶት፣
መላ ቅጡ ጠፍቶት፣
እሳቱ ...ተፋጅቶት፣
ግብዝ ገላ ይዞ፣
ለጥፋት ተጋብዞ፣
ድግሱ እንዳበቃ፣
በበሽታ ሳንቃ፣
እቅ ብላ ሰርቃ፣
ስቅ ስታበቃ::

---

## የሶፍት ላይ ፍቅር

ለዓይኖቿ ሳስቼ
እንዳያንፀባርቃት፣
ወረቀቱ በዝቶ
እንዳያስጨንቃት፣
እንዳትዘናጋም ስለሳሳሁላት፣
ለቀስላሳ መልሷ ምሳሌ
እንዲሆናት፣
አለመተዋወቅ ወይ
አለመግባባት፣
ለወረውርላት ከዚያው
ካለችበት
ፍቅሬ "ናብኪን" መስሏት
ተናፈጠችበት::

ጌታቸው ዳውድ
3rd Cooperative Accounting
and Auditing

# ውብት

## ድንግልና ውበት :ኩራትና ጤናም ጭምር ነው::

አምባሳደር ዘመን ተፈራ

አምባሳደር ዘመን ተፈራ ተወልዳ ያደገችው በምስራቂቷ የአገራችን ክፍል በሱማሌ ክልል ርዕሰ መዲና በጅጅጋ ከተማ ነው :: የአጠቃላይ አንደኛ ደረጃ ትምህርቷን ቅዱስ ዮሴፍ በተባለ የግል ት/ቤት ተማረች 9ነኛና 10ረኛ ክፍልን ደግሞ በጅጅጋ ከ/ሁለተኛ ደረጃ ት/ቤት ተከታተለች :: የቅድመ ኮሌጅ ( ኘሪፓራቶሪውን) ትምህርት በሐረር ከተከታተለች በኃላ አመርቂ ውጤት በማስመዝገቧ በዓለማያ ዩኒቨርስቲ ተመድባ በመማር ላይ ትገኛለች :: ለመሆኑ ይቺ መንፈሰ ጠንካራ ወጣት እንዴት አምባሳደር ልትሆን ቻለች ? - ወደ ቃለ ምልልሱ

በኢብራሒም ሰይድ

**ራዕይ:-** የት/ቤት ሂወትሽ ምን ይመስል ነበር?

**ዘመን :-** እስከ ስምንተኛ ክፍል የተማርኩት እዚያው ጅጅጋ ቅዱስ ዮሴፍ በተባለ የግል ት/ቤት ነው:: የተለያዩ ድራማዎች: ስነፁሁፎች ላይ ተሳትፎ የምናደርግባቸው በርካታ ምቹ ሆኔታዎች ስለነበሩ በወላጆች ቀን በአል ላይ ስራዎቻችንን እናቀርብ ነበር:: ያ ማለት ደሞ በኔ ጭንቅላት ውስጥ ታላቅ ሚሞሪ ጥሎ ያለፈ ትዝታ ነው::

**ራዕይ:-** አስተዳደግሽ ምን አይነት ነው በቤተሰብ ዘንድ ነፃነት አለሽ ወይስ ቁጥጥር ይደረግብሻል?

**ዘመን :-** ልክ እንደማንኛ ውም ልጅ የቤተሰብ ቁጥጥር አለ:: ስንት ሰዓት ወደ ቤት መግባትና መውጣት እንዳለብኝ የተወሰነ ሰዓት አለ ሪስትሪክትድ ነው:: ግን ለምሳሌ ጓደግቼ ጋር ለመሄድ ብፈልግ አስፈቅጄ ስለምወጣ ያን ያህል አቅጣጫውን የሳተ ቁጥጥር አይደረግብኝም:: ምክንያቱም እኛ ቤት በግልጽ ውይይት እናምናለን::



ራዕይ:- ፍቅር ይዞሽ ያውቃል?

ዘመን :-( ረጅም ሳቅ) ይህ ጥያቄ ይለፈኝ::

ራዕይ:- ይህ ጥያቄማ በፍጹም ማለፍ የለበትም:: ምክንያቱም ማንኛውም የህብረተሰብ ክፍል አንድ ቀን ሳይወድ በግዱ ለፍቅር ይንበረከካል:: አንቺስ?

ዘመን :- በፍቅር ስለመያዜ እርግጠኛ ሆኜ ስለማላውቅ ይህን ጥያቄ ለመመለስ ይከብደኛል::

ራዕይ:- መቼስ ምን ይደረጋል እንግዲህ እርግጠኛ ስትሆኚ ታጫውቺኛለሽ:: አሁን ወደ ሌላ ጉዳይ ልለፍና እስኪ ስለ «ሐረር ሽልማት 97 » ፕሮግራም ንገሪኝ

ዘመን :- ውድድሩ በጣም ደስ ይላል:: በጣምም ፈታኝ ነበር:: ሁላችንም ድንግል ( virgin ) በመሆናችን በጣም ሃይለኛ ፉክክር ይስተዋል ነበር:: ምክንያቱም ሁላችንም አንድ አይነት ነገር ይዘን compute ስናደርግ ያስጨንቅ ነበር::

ራዕይ:- የአምባሳደርነቱን ሹመት የሰጠሽ አካል ማነው?

ዘመን :- በመጀመሪያ ደረጃ ፕሮግራሙን ያዘጋጀው የሐረሩ የኤድስ መከላከያና ማህበራዊ አገልግሎት ድርጅት ( OSSA) የተባለው መንግስታዊ ያልሆነ ግብረሰናይ ድርጅት ነው:: በዚያ ውድድር ላይ መጀመሪያ ላይ እንደ ( Beauty Contest ) አይነት ስለነበር ቁመት ምናምን ታይቶ ነበር:: በዚህ ምክንያት አንዳንዶቹ መስፈርቱን ባለማሟላታቸው ከውድድሩ ከሚቀሩ ተብሎ ሁላችንም ደናግላን ተወዳደርን:: በበኩሌ ለዚህ ፕሮግራም በጣም ብዙ ለፍቻለሁ:: ምክንያቱም ጊዜው ክረምት በመሆኑ ብሬክ ነው:: ስለዚህ ለውድድሩ ስል ከጅጅጋ ሐረር መመላለስ ነበረብኝ በመጨረሻም በውድድሩ በማሸነፌ የከፍተኛ ትምህርት ተቋም አምባሳደር ተብዬ ለመሸለም በቃሁ::

ራዕይ:- ሽልማቱ ምን ነበር? . . . የሙባይል አፖራተስ: ወርቅ:ብዙ ሺ ብሮች. . .

ዘመን :- በፍፁም አምስት ሳንቲም አላየሁኝም:: ያው ስሙን ብቻ ነው የተሸለምኩት::የሚገርምህ ነገር ከጅጅጋ ሐረር እንኳን የምመላለሰው የተለያዩ ወጪዎችን የማወጣው ከራሴ ኪስ እንጂ አበል ታስበልኝ አይደለም:: ያም ሆነ ይህ እኔ መጀመሪያውንም ስወዳደር እነዚህን ነገሮች Expect አድርጌ ስላልተነሳው አሁን የምትላቸውን ነገሮች ባለመሸለሜ አይቆጨኝም::

ራዕይ:- በአሁኑ ሰዓት በአለማያ ዩኒቨርስቲ የመጀመሪያ አመት ተማሪ ነሽ: የትኛው ዲፖርትመት ውስጥ ነሽ?

ዘመን :- ፋካሊትዬ Business and Economics ሲሆን ዲፖርትመንቴ ደግሞ ኢኮኖሚክስ ነው::

ራዕይ:- የዩኒቨርስቲ ሂወት ከውጪው ጋር ያለው ልዩነት ምንድነው?

ዘመን :- እየህ እዚህ ካምፖስ ውስጥ በዚህ ግባ በዚህ ውጣ ብሎ የሚቆጣጠርህ ሰው የለም እዚ የሚቆጣህ እናት የሚመክርህ አባት የለህም ስለዚህ ሁሉም ሐላፊነት የወደቀው አንተው ላይ ነው:: ያ ማለት ደሞ ዩኒቨርስቲ የራስህን ሂወት ራስህ የምትመራበት ቦታ ነው::

ራዕይ:- የካፌው ነገርስ?

**«የፊልም ዳይሬክተርነት ሙያ መማር እፈልጋለሁ »**

**ዘመን** :- ( ሳቅ) ካፌው አንዳንድጊዜ ደህና ነው:: አንዳንዴ ደሞ ይበላሻል:: በአንድ ቃል እንዲህ ነው ብሎ መናገር ቢከብድም ጥሩነው ማለቱ ሳይሻል አይቀርም::

**ራዕይ**:- የወደፊት አላማሽ ምንድነው?

**ዘመን** :- መጀመሪያ በዚህ በያዝኩት ፊልድ ዲግሪዬን ማግኘት እፈልጋለሁ:: የእግዚአብሄር ፈቃድ ከሆነ ግን የፊልም ዳይሬክተርነት ሙያ መግር እፈልጋለሁ::

**ራዕይ**:- በት/ቤት ሂወትሽ በጣም ዝቅተኛና ከፍተኛ ውጤት ያመጣሽባቸውን አጋጣሚዎች አስታውሽኝና ያደረብሽን ስሜት ግለጭልኝ?

**ዘመን** :- ዝቅተኛ ውጤት ያመጣሁት 10ኛ ክፍል ማትሪክ ላይ ነው:: እራሴን እንደጠበኩት ያላገኙሁበት በመሆኑ በጣም አልቅሻለሁ ትንሽ ሆኜ ኤለመንተሪ ማለት ነው:: ከአንደኛ እስከ ሶስተኛ ወጥቼ ስሸለም ደስታዬ ወደር አልነበረውም::

**ራዕይ**:- በትርፍ ጊዜዎችሽ የምታዘወትሪያቸው ሆቢዎች ምንምን ናቸው?

**ዘመን** :- ፊልም ማየት: መፀሐፍ ማንበብ: ግጥም መፃፍ. . . እንዲያውም አሁን ግጥሞቼን አልያዝኩቸውም እንጂ አሳይህ ነበር::

**ራዕይ**:- ሙሉ ስምሽ ማን ይባላል?

**ዘመን** :- ዘመን ተፈራ ፍሰሃ

**ራዕይ**:- በከፍተኛ ትምህርት ተቋም የ1997ዓ.ም የመታቀብ አምባሳደር ነሽ:: አምባሳደርነትሽ እስከመቼ ይዘልቃል? . . . ነው ወይስ የእድሜልክ ነው ?

**ዘመን** :- አዲሶቹ ተወዳድረው እስከሚያሸንፉ ድረስ ከዚያ በሁዋላ ግን ወይ እኔ ድጋሚ መወዳደር አለብኝ:: አለበለዚያ ለተተኪዋ ማስረከብ አለብኝ::

**ራዕይ**:- ውበትን እንዴት ትገልጭዋለሽ?

**ዘመን** :- ውበትን በሁለት እከፍለዋለሁ:: ውስጣዊና ውጫዊ ውበት አለ :: ውጫዊው ያው አይን : ከንፈር : ፀጉር ምናምን ተብሎ እንደሚከፈለው ነው::

**ራዕይ**:- እጅና እግርም አሉ እኮ

**ዘመን** :- ( ሳቅ) አዎ እግር ምናምን: ውስጣዊው ደሞ በታታማኝነት:እስተዋይነት እና እግዚአብሄርን መፍራት ነው::

**ራዕይ**:- አንቺ ምን ያህል ውብ ነኝ ብለሽ ታስቢያለሽ

**ዘመን** :- እኔ እንጃ! ይህን ጥያቄ አስቤበት አላውቅም ሰው የራሱ የሆነ መልክ አለው:: ለራሱ ውብ ነው እሱን የሚመስል ሌላ ሰው የለምና:: ሰውን ከሌላ ሰው ጋር አወዳድረህ አንተ ውብ ነህ አይደለህም ማለት አይቻልም:: እኔም የራሴ የሆነ መልክ አለኝ: እኔን እመስላለሁ ( ሳቅ)

**ራዕይ**:- ግን በቁንጅና ውድድር ላይ የተለያዩ ተወዳዳሪዎች ቀርበው አንድዋ የግድ ውብ ሆና ትመረጣለች:: ስለዚህ ሰው ሁሉ ውበት ቢኖረውም አንዱ ከሌላው ይበልጣል አነቺ ምን ያህል ውበት አለኝ ትየለሽ?

**ዘመን** :- I don't know . . . ይህን ያህል ውብ ነኝ አልልህም: አስጠላለሁም አልልህም: በቃ . . . medium አታውቅም ?

**«ይህን ያህል ውብ ነኝ አልልህም »**

ራዕይ:- ከውስጣዊና ውጫዊ ውበትሽ የትኛው ይበልጣል?

ዘመን :- ካለኝ ባህሪ አንፃር ውስጣዊ ውበቱ የማበልጥ ይመስለኛል::

ራዕይ:- አምባሳደር እንደመሆንህ መጠን ሃላፊነትሽን ምን የህል እየተወጣሽ ነው?

ዘመን :- Ok! በተለያዩ ቦታዎች ላይ ሰርቻለሁ:: አስተምሬአለሁ:: በተለይ በጅጅጋ: በሐረር: አሁን አለማያ ዩኒቨርስቲ እንግዲህ አዲስ ተማሪ ነኝ ገና ብዙ መስራት አልቻልኩም:: ግን ከለመድኩኝ በኋላ ከእናንተ ጋር ወይም ከተለያዩ የፀረ ኤድስ ክለባት ጋር በመሆን ግቢ ውስጥ እስካለሁኝ ድረስ ብዙ መስራት ይጠበቅብኛል ብዬ አምናለሁ::

ራዕይ:- በድንግልና መቆየት ፋይዳው ምንድነው ?

ዘመን :- ጥሩ ነገር:: አንደኛ ኤድስን ለመከላከል አስተዋጽዎ አለው:: በእርግጥ አንዲት ልጅ ድንግል ስለሆነች ኤድስ አይዛትም ማለት ሳይሆን ድንግልና ማለት መታቀብ ነው:: መታቀብ ደሞ ኤድስን ለመከላከል ከተቀመጡት መንገዶች አንዱና ትልቁን ሰፍራ ይይዛል - ሁለተኛ ያለው መንፈሳዊ ደስታ ቀላል አይደለም:: ቨርጂን ሆነህ ማግባት ያለው ሳይኩሉጂካል እርካታ ለሁሉም ግልጽ ነው:: ምክንያቱም ጭንቅላትህ ቨርጂን ነኝ ብሎ ስለሚያስርክ አጋጣሚዎች በሚፈጥሩት ስህተት እንዳትጉዳ ይረዳሃል:: እንደ ባህልም ካየኸው ደሞ በድሮ ጊዜ ድንግልና ይከበራል:: አንዲት ልጅ ከጋብቻ በፊት ምንም አይነት ነገር አታደርግም::



*በግ ተራ መቆሙ በራሱ አያስኮንንም ግን ስምን ምክንያት ነው የምቆመው ብሎ ራስን መጠየቅ ብልህነት ነው »*

ራዕይ:- አሁን ከሐረር ወደ ሐመር ልውሰድሽና በሐመር ብሄረሰብ ባህል መሰረት አንዲት ልጅ ከማግባቷ በፊት ከበርካታ ወንዶች ጋር ኢቫንጋዲ በተባለው የጭፈራ ስርአት የግብረ ስጋ ግንኙነት ማድረግ አለባት:: አለበለዚያ ግን በእነሱ ባህል ከነድንግልና ማግባት ነውር ነው:: ስለዚህ ብሔረሰብ የምትይን አለ?

ዘመን :- ድንግልና ውበት: ኩራት:ጤናም ጭምር ነው አሁን ሐመሮች እኮ ድንግል መሆንና

ወደ ገጽ25 ዞሯል

# Techno - page



## Impact of information and communication technology (IT) in Education.

Dr. Luis Bello, Faculty of Education, Alemaya University,
lbello@softhome.net

### Introduction

The Internet, the mobile phones and the satellites are making a great impact in the way we live and behave, using the technologies mentioned before you don't need to be present or travel to a particular place to have a first hand information or experience.

I still remember once I was planning to travel to another country by myself, before I did it, I went to the Internet and did some search for tips and advices about traveling there, and I was really impressed by the information posted and the coincidence with the real things I experienced when I was there.

In this paper I would like to share with you some of my ideas about using Internet, mobile and satellites in the field of Education.



Dr. Luis Bello, PhD, Cuban staff at Alemaya University, he has being teaching computer course for the last 20 years and also supervising research works about using technologies in Education.

### Internet

Is becoming everyday a powerful tool for teacher and students, now days it is almost impossible to think that any school can be successful without having an Internet access, Internet is a source of information where both the teachers and the students can find almost everything regarding the current topics they are learning.

The e-mail is one of the Internet services that help a lot to keep in touch among colleagues from others places and even among the students, many information can be send and receive using this service without taking a lot of time.

The **Chat room** is another service very important to have a kind of communication with other persons but the difference with the e-mail is that you can have this exchange in a real time (on line) you don't need to wait until the message is processed by the server. This is very useful for having a meeting or a conversation with one or many persons at one, in education you can use this service for having a kind of on-line class or seminars, the students don't have to be in a particular place to address to you or raising any question.

The use of searching engine like **Google** (www.google.com) helps to find a lot of information in almost any language available all over the places, you just type the keyword for the information you are looking for and in a few seconds a list of places where you can find something related to it are immediately displayed, it doesn't mean that you will have access to all of the information but at least you will know if somewhere or someone knows about it, so information aren't free on the internet or just restricted.

The Google site allows you to configure it so you can do some searching in a particular language or with a particular filter, making the search more refined.

The are currently many internet portal like **Yahoo** (www.yahoo.com), that allow you to personalize you web site and even to store data in they server that make it available practically everywhere you go. I found the personalized option very useful, because they give me the freedom to select the information I want to check like which news I want to read.

Another feature that Internet offers you is that you can apply on-line for a new job, fill any forms or registered using the electronic formats available in many of the sites, this option help to reduce the time that information takes to get to the potential place you are submitting.

One of the negative aspect about using Internet is some people become too addicted to the Internet that they can't hardly have any social life and a few of them like to do some negative things to others people connect to the network, the other thing I believe is overwhelming on the Internet is the amount of advertisements send everyday to you e-mailbox or just ads that pop up every time you access to particular place. Lately some programs c alled spywares or adwares, can install in your computer and feedback with information about you like which sites are the most visited by you, how many time you spend on the Internet, etc.

**Mobile phones**

Is emerging as a new technology that is trying to catch the facilities that computers are offering, with the new mobile devices you can be in touch with your coworkers and students practically everywhere you are and that help to exchange information, beside you can also exchange pictures or text messages, new services for having I nternet a ccess a re i n the process of being offering by the companies.

Some of the use of mobile in Education can be for using some dictionaries on line and for checking the spelling of some words in more than one languages, others countries are offering a service that allow you to ask questions an receive the answer in a short period of time.

Some of the uses mobile phones:

- Communication among colleagues, students, authorities.
- Electronic Agenda
- Sending Text or Picture message.
- Consulting information like dictionaries or databases.
- Receiving news directly on the phone.

**Satellites**

The use of satellite have the advantage that you don't need to connect it with direct line from the emitting center to the receiver, because the signal goes through the air, it is very helpful particularly for remote areas. The importance of using satellite is that you can transmit the same program to every students without loosing quality in the process, because they all will receive the same information, this improve the learning and general speaking the cultural background of the students.

The use of satellite for education can be good or bad, depend of the use of it, if we allow the students to use it in a passive way, without reflecting about the programs they watched, them is a bad use of it, we need to use the programs but at the same time helping the students to have an active attitude and to be involve in real situations.

Page 2 de 3

**Some positives and negatives aspects of using technology in education.**

**Positives**

- The information is standardized in a particular format, all the receivers will get almost the same information with a little of distortions or modification, that help to have the same outcome in the students.
- A lot of update information can be accessed, transferred and printed to many students and instructor in a short period of time like books, papers, reports, news.
- The relationship and communication among the students and instructor are stimulated through this media.
- Increase the students' motivation and reduce the load work of instructors, reducing the time spent in monotonous tasks.
- Most of the devices are relative portable to carry to classroom like the computers and mobiles.

**Negatives**

- No all the information is suitable for all the people receiving it and at some point can be even produce a complete negative effect. The role of the teacher is to select, present and explain more in case it is necessary.
- Not all the people and countries can afford to use the technology due to the some of the devices (Plasma Screen) or services (Internet) are quite expensive, beside the access to the electricity is not always available.
- The same technology can be used for many different aims, in other words can serve to disseminate information that can be offensive to the moral, politics or religious belief of individuals or groups.
- There is a need of small training or previous knowledge for all the users in order to use efficiently, otherwise can be underused or improperly manage with the consequence of future operational failures.
- The source of information and services are mainly coming from the developed countries, which is not always applicable to poor countries or less developed, the cultural references can not be suitable for a particular region, group or society.

**Conclusion**

Using the information and communication technology like Internet, Mobile phones and satellites are very important tools for education, the teachers and students will have to update their knowledge and skills and get familiar with this technology. The teacher role is going role will be changing slowly, the teacher will not be substitute

## ውስጣዊ ውበትን...

ከገጽ 5 የዞረ

ውስጣዊ ውበት ብቻውን ፋይዳ እንደሌለው የአደባባይ ሚስጥር ሆኖ ሳለ ውስጣችንና አካባቢያችን ሲቆሽሽ ማየቱ ያሣፍራል:: ቆሻሻን የፈጠረው ኮ የውስጣዊ ውበታችን ማነስ ነው ገባህ? ውስጣዊ ውበት ቢኖር እኮ የፊታችን ውበት ምን እንደሚመስል ኖረቢው ማየት አችላለህ? እና ከላይ አምረህ ተሽቀርቅረህ ውስጥህ ቆሻሻ ከሆነ ውበትና ቆንጅናው ምኑ ላይ ነው እስኪ አንተ እራስህ መስክር ቤትህ ዝርክርክ ብሎ ሲውል አይጨንቅክም? በቃ Like እንደዛው ነው:: እኔ እንደሚመስለኝ አካባቢን ማጽዳት ከውጭ እርዳታ እና ከድህነት ጋር ሊያያዝ አይገባውም:: አንድ መጥረጊያ ገዝተህ አካባቢህን ብታፀዳ ገንዳዎችን ተባብረህ ብትደፋኮ ይሄ በራሱ ታላቅ ድል ነው ውበት ማለት ደሞ ይ! ነው:: የግድኮ አንተ ቤትህንና ጊቢን ውብ ለማድረግ በተለያዩ የአበባ ዝርያዎች መትከል አይጠበቅብህም:: ያለችህን ደሳሳ ጉጆ ብትጠርግ አካባቢህን አስዋብክ ማለት ነው:: ሠፈርህ ቆሻሻ ሆኖ ቤትህ ብቻ ቢያምር ጥሩ ስለሆነ ሠፈራችንንም ማፅዳት አለብን::

**ራዕይ:-** መዲናችን አዲስ አበባ የታላላቅ ዲፕሎማቶች መቀመጫ እንደመሆኗ መጠን ንፅህናዋ ብዙም አያኩራም በዚህ ጉዳይ ላይ ምን አስተያዬት አለሽ? ስለሌሎች ከተሞችስ?

**ወሰን :-** አዎ የአዲስ አበባ የንፅህና ነገር አሳሳቢ ነው አሁን ግን የተፈለገውን ያህል ባይሆንም ለውጥ እየታየ ነው:: ቢሆንም በጣም ብዙ ይቀረዋል:: ሌሎችን በተመለከተ . . . ሐረርን አይቻለሁ እንደሚታወቀው ሐረር በየመንገዱ ላይ ከተማ ውስጥ ሁሉ ሣይቀር ሽንት ይሸናል:: እዚህ ገበያው ሐረር በር ወረድ እንዳልክ መአት ሽንት ይሸናል:: ማዘጋጃ ቤቱ ላይ ሆነህ ስታየው ሽንት የተሸናበት ቦታ የተለየ ገጽታ ይዞ ታየዋለህ:: ሽንት ማለት ደግሞ በጣም አደገኛ ነገር ነው:: ለጉንፋን አደገኛ መንስኤ ነው:: ፀሃይ ሲነካው ልጆቹ ይታመማሉ : እና የሐረር ጉዳይ በጣም ከፍተኛ ጽዳት ያስፈልገዋል::

**ራዕይ:-** ውብ ከሚባሉ ከተሞችስ?

**ወሰን :-** ሐረርን አይቻለሁ: ጉንደርን አይቻለሁ:ጅጅጋና ባህርዳርንም አይቻለሁ:: እስከአሁን ግን እንደድሬደዋ ውብና የፀዳች ከተማ አላጋጠመኝም:: የምትታይም ሐገር ናት:: እናተም እራሡ ልትፈርዱ ትችላላችሁ:: ድሬደዋ ለውጥ አላት: ሰርታለች:: አርፋ ትቀመጥ ማለቴ አይደለም በጣም ብዙ ይቀራታል:: ግን at least ለመታየት የምትበቃ ከተማ ናት:: ድሬደዋ ሽንት ሲሸና አይቼ አላውቅም::

**ራዕይ:-** የእናንተ ፕሮጀክት ሐረር ላይ ምን እየሰራ ነው?

**ወሰን :-** ሐረር ላይ ከራስ ሆቴል ፊት ለፊት ያለው ቦታ የልጅ እያሡ ኮቴ ያረፈበት ቦታ ነው:: ይህ ማለት ደሞ ታሪካዊ ቦታ ነው:: ይዘቱን ሣይለውጥ ይህን የተረሣ ታሪክ በማደስ ለትውልድ ልናስተላልፍ በሚያስችለን ስራ ላይ ነን:: የጠፋውን ታሪክ መመለስ ቀላል ነገር አይደለም:: የታችኛው

ወደ ገጽ 22 በዞረ

ፋውንቴን እታች ማዘጋጃ ቤቱ ጋር ያለው < ውሃችን ተስፋችን > ብለን የምንሰራት ትንሽ ግን የሐረርን የውሃ እጥረት በማሣየት በጉ አድራጊዎችና መንግስትን ልታባንን የምትችል ነገር ናት::

ራዕይ:- ስመሆኑ ከጋሽ አበራ ጋር በሰርግ ነው የተጋባችሁት?

ወሰን :- በሰርግ እንኳን አይደለም የተጋባነው:: እኛ ቤት ሽማግሌ ተላከ ተፈራረምን:: በቃ ሰርግ አላደረግንም:: ሰርግ ለመደገስ በጣም ሰፊ ጊዜ ያስፈልግሐል:: እኛ አሁን ከስራችን ጋር በተያያዘ ድሬደዋ ተጠራን: ጅጅጋ ተጠራን: ሐረር ተጠራን: ሰርጉ ነገ ቀስ ብሎ ይደርሣል:: የዛሬው አንገብጋቢው ጉዳይ ለወጣቱ የስራ እድል መፍጠር ነው:: ሰርግ የማድረጉ ሐሳብ አለ:: ነገር ግን ለስራው ቅድሚያ ሰጥተናል::

ራዕይ:- በአብዛኛው ሴቶች ያለሰርግ ማግባትን አይፈልጉም:: ለእነሱ የምትያቸው አለ ወይስ አንቺም የነሱን ሃሳብ ትጋሪያለሽ?

ወሰን :- ሰርግ የፍቅር መግለጫ: የመተሳሰሪያ ድልድይ እንጂ የሆይሆይታ አይደለም:: ሰርግ ማለት የእኛን አንድነት ቤተሰብ: ወዳጅ ዘመድ ይይልን የምንልበት መድረክና ጊዜ እንጂ ዛሬ በሆይሆይታ ተጋብተህ ነገ የምትፋታበት አጋጣሚ መሆን የለበትም:: የኛ ሃገር ባህሉም ልማዱም ስለሚከብድ ነው መሰለኝ ሰርግና ድግስ ላይ የለን አመለካከት ከፍተኛ ነው:: አንተ ባለህ ለምን ሻይና ዳቦ አይሆንም: አድርገህ ፍቅርህን መመስረት እንጂ ሰው በላ አልበላ ብሎ አላስፈላጊ ጭንቀት ውስጥ የምንገባበት አጣብቂኝ መሆን የለበትም - ሰርግ:: በአሁኑ ሰዓት በዚህ የከፋ ዘመን ተደብቆ መኖር ሂወትን ጠብቆ መኖር: ሰርግ ማለት ለሴቶች እህቶቼ የማስተላልፈው መልክት ቢኖር ወልዳችሁ ሳሙ: ጋብቻችሁ የአብረሃም የሣራ ይሁን እላለሁ እንጂ ሰርግ አርጋችሁ አግቡ ብዬ አልመክርም:: ዋናው ነገር በሰላምና በጤና የምትኖር ከሆነ እድሜ ልክህን እየሰረግክው ትኖራለህ ነው የምለው::

ራዕይ:- በአሁኑ ሰዓት አብዛኛው ተጋቢ ከጋብቻ በፊት የደም ምርመራ ያደርጋል:: እናንተስ?

ወሰን :- አዎ መመርመር በጣም ያስፈልጋል:: እኛ እንኳን አልተመረመርንም እሱ ከአስር አመት በፊት ከአሜሪካ ሲመጣ ተመርምሮ ነበር:: ከዚህ በፊትም ሲሄድ ተመርምሮአል እና ጤነኛ ሣትሆን ወደዚህም ወደዚያም መሄድ አትችልም እና እሱ ይህን ሁሉ ተመርምሮ ነው የመጣው:: እኔን ደሞ ሲያየኝ ያልተጠራጠረኝ እንደኛ የቤት ልጅ ነኝ: ከቤት ውጥቼ አላውቅም:: ባጠቃላይ ከማንም ጋር ግንኙነት ሣይኖረኝ ነው ያገኘኝ:: ተማሪ እያለሁ ማለት ነው:: አሁንም ደግሞ ልንመረመር እንችላለን:: HIV /AIDS ዛሬ እና ነገ ስላልከው አይደለም አሁን ልኖርብህ ይችላል::

ራዕይ:- ሣትመረመሩ ነው የተጋባችሁት?

ወሰን :- አዎ ተማምነናል:: ሳንመረመር ብንጋባም: ቢኖርብንም ከእግዚአብሄር

ወደ ገጽ 27 ዞሯል

# Academic affairs



ትምህርት ነክ የሆኑ ወቅታዊ ጉዳዮችን የምንዳስስበት አምድ ነው::

## ኢንተርናሺናሊ ጆብ ማርኬት ያለው Soil &Water Engineering ነው:: ዶ/ር ጠና አላምረው

**በዓለማያ ዩኒቨርስቲ ውስጥ አዲስ ከተከፈቱ ዲፓርትመንቶች መካከል soil & water engineering አንዱና ዋነኛው ነው :: እዚህ ዲፓርትመት ለመግባት ጥሩ ውጤት ያስፈልጋል በሌላ አገላለፅ ሰቃይ መሆንን ይጠይቃል :: ይሁን እንጂ የስሙ በየጊዜው መለዋወጥ ተማሪዎችንና የትምህርት ክፍሉን ሲያወዛግብ ቆይቷል :: በዚህ ጉዳይ የዩኒቨርስቲውን የትምህርትና ምርምር ም/ፕሬዝዳት ዶ/ር ጠና አላምረውን አነጋግርናቸዋል ::**

በEbrosen ( Journal –Engineer )



**ራዕይ** :- soil & Water Engineering **ወደ ድሬደዋ የመሔድ እድሉ ምን ያህል ነው ?**

**ዶ/ር ጠና:-** swme እና food science ወደ ድሬደዋ አንልካቸውም:: ምክንያቱም የድሬደዋ ዩኒቨርስቲ ኮሌጅ ወደፊት እራሱን ስለሚችል እነዚህን ጠካራ ፕሮግራሞች ማጣት አንፈልግም ወይ እዚሁ ወይም ሐረር ዋናው ዩኒቨርስቲ የቴክኖሎጂ ፋካልቲ ስለሚከፈት ማቴሪያሉንም ሰፖርትን በተመለከተ ወደፊት የሚመቻች ይሆናል:: በተለይ እነዚህ ሁለቱ ፕሮግራሞች ሊያድጉ የሚችሉ ናቸው:: ሊሰፉ የሚችሉ ናቸው:: to wards environment, towards land resource and GIs በኩል ኤክስፓንድ የሚያደርጉ ጠንካራ ፕሮግራሞች ናቸው::

**ራዕይ:- ዲፓርትመቱ አዲስ በመሆኑ አንድ የ** soil & water Engineering **የ**BSC **ተመራቂ ወደፊት የሚገጥመው የስራ ዕድል ምን ያህል ነው?**

**ዶ/ር ጠና:-** እንግዲህ soil & water Engineering ስንል በውስጡ ብዙ ነገርን ያካተተ ነው:: ቢዚካሊ ኢትዮጵያ ማደግ ካለባት ወይም ደግሞ የኢትዮጵያ ህዝብ እራሱን መቀለብ ካለበት አግሪካልቸሩ ማደግ አለበት:: ለማደግ ደሞ ኢንተስፊኬሽን ያስፈልገዋል:: በኛ ሐገር ደሞ አግሪካልቸርን ኢንተስፋይድ ለማድረግ ምርጥ ዘርና ማዳበሪያ ይኖር ይሆናል::

ወደ ገጽ 26 ዞሯል



# የብዕር ጠብታዎች

### እንደገና

ወራጅ አለ እያልኩት
እየወተወትኩት
አሳልፎ ቢጥለኝ ያ! መኪና
ጉዞዬን ጀመርኩት ወደኋላ
እንደገና::
(ጽጌሬዳ ጉንፋ)

### ሆዳም

የያዘችውን ሁሉ
ንብረትዋን በተርታ
ሣታኝክ ብትውጠው
ጠዋትና ማታ
መሬትን ታዘብኳት
የሚውልባት አጥታ
እራቁትዋን ስትቀር
· ድፍን ትውልድ በልታ::
(አብዱልአዚዝ ዲና)

### ስቀሽ ከገደልሽኝ

ጦር ሰብቀሽ ሳትስቢ
ሤራን ሣታስቢ
ስቀሽ ከገደልሽኝ
ለብቻዬ ልኑር
አልይሽ ትራብኝ::
/ መለሰ ጌታነህ /

### « I have lost »

I have lost
My soul's companion
A life linked with my own
And day by day
I miss her more,
As I walk through life alone.
(Temesgen Gemechu)

አቤት ሰወዳችሁ
ከነ ሙዶቻችሁ
የግቢ ጓዶቹ ትመቹኛላችሁ
ካፌ ስንገናኝ ወይም ላይብረሪ
« እንትናዬ ማነሽ አናግሪን አትፍሪ »
ብላችሁ ቀልዶችን ስትጀማምሩ
እሺ እኔም ላውራ በሉ እንግዲ አውሩ
ብዬ ተናግሬ ሣልጨርሰው ቃሌን
አለቀ ተግባባን በአንዴ አንድ ሆንን::
/ ከእመቤት ወርቅነህ/
(ለምወዳችሁ ለአለማያ ዩኒቨርስቲ ወንዶች በሙሉ)

**መ ሀ ላ**

ጎመንንም ላልተው
... ስላጣም ላላጠላ
ጫትን ግን ላልነካ
... ገባሁኝ መሀላ
ፍየል ከሳኛለች
... ቅጠል በላህ ብላ

ኢብራሂም ሰኢድ
(Swme)

# ድንግልና . . .

ከገጽ 17 የዞረ

አለመሆናቸው አይደለም ጉዳቱ፡ በአሁኑ ሰዓት አስብ እስኪ የኤድስን ስርጭት:: ይህ ነገር ደሞ ከእነሱ ባህል ጋር አይሄድም:: ከዚያ መሐል እኮ አንዱ የኤድስ ቫይረስ በደም ውስጥ ቢሮርበት ምን ያህል ህዝብ እንደሚያሲዝ መገመት አያዳግትም ስለዚህ ይህ ነገር ኢቫንጋዲ ጭፈራ ላይ የሚታየው ጥንቃቄ የጐደለው ወሲብ ጉዲነቱ እንጂ ሌላ ጐኑ አይታየኝም:: ምክንያቱም ዘመኑ ተለውጦአል:: በሽታውም እንደዚያው፡ even ድንግል መሆንህ አይጠበቅም፡ አንተ የኔ ከምትለው ሰው ጋር ተማምነህ መኖርም እኮ ትልቅ ነገር ነው ::

**ራዕይ:-** ስለጠነ በሚባለው በአሁኑ ትውልድ በአብዛኛው ድንግልና የፋራ ነው:: ተብሎ ይታሰባል በዚህ ጉዳይ ላይ ምን አስተያየት አለሽ?

**ዘመን :-** እኔ ቨርጅን ነኝ ብዬ በማስተምርበት ሰዓት ሙድ አልገባትም . . . ወዘተ አይነት ነገሮች እንዲሁም በጣም ብዙ ተቃውሞ፡ ስድብ እንደሚያጋጥም መጀመሪያውንም አላጣሁትም:: ግን ከኛ ቀጥሎ የሚመጣው ተውልድ ምን አይቶ ይማራል? እና ትንንሽ ልጆች እኛ መጀመሪያ ሆነን ካላሳየናቸው የህብረተሰቡን ወሬ ሰምተው ከግንዛቤ ማነስ አኳያ ለድንግልና አመከላከትና ክብር በመዘንጋት ለችግር ይዳረጋሉ:: በሌላ አገላለጽ ምንም አይነት አድናቆት ከሌለው ከታች የሚመጡት ልጆች በአመለካከት ብቻ ድንግልናን እንደተራ አድርገው ይቆጥሩታል:: ያ እንዳይሆን ደግሞ እኔ እዚህ ጋር ቆሜ አስተምራለሁ:: ምንም እንኳን እኛ የመጀመሪያዎቹ እየተጠላንም፡ እየተሰደብንም ቢሆን አስተምረን ለታችኞቹ አርአያ በመሆን ሃላፊነታችንን መወጣት ግድ ይለናል አሁንም በድጋሚ የምነግርህ ነገር ቢኖር ድንግልና ክብር ነው::

**ራዕይ:-** ወደፊት የትዳር (የፍቅር) ጓደኛሽ ሊሆን የሚችለው ሰው ምን አይነት ነው? ድንግል መሆን አለበት?



**ዘመን :-** ድንግል ይሁን አይሁን የሚለው ነገር አያሳስበኝም:: ግን ከሁሉም በላይ እግዚአብሄርን ቢፈራ ደስ ይለኛል:: ዘመን ታየኛ ለች ወይም አታየኝም ብሎ ሳይሆን እግዚአብሄርን ፈርቶ ወይም ኑሮአችንን ፈርቶ የለም? . . . በቃ መስፈርቴ ያ ነው::

**ራዕይ:-** በግ ተራን እንዴት አገኘሽው?

**ዘመን :-** ምንም እንኳን ለበግ ተራውም ለምኑም አዲስ ብሆንም እዚያ ቦታ ላይ መገኘት ምንም አያስደስተኝም:: በግ ተራ መቆሙ በራሱ አያስኩንንም ግን ለምን ምክንያት ነው የምቆመው ብሎ እራስን መጠየቅ ብልህነት ነው:: እከሌ ለምን ቆመ እከሌ ለምን አልቆመችም ብሎ በዚያው በሰው ላይ ግምት ማውሰድ አይቻልም::

ወደ ገጽ 28 ዞሯል

ከገጽ 23 የዞረ

ግን በእኛ ሐገር ሁኔታ ለዚያውም የዝናቡ ሁኔታ አንጎ ሬዲክቴብል በሚሆንበት ሰዐት ላይ irrigation, Water Resources concentration ,these are the key areas, Key areas of intervention ናቸው:: እና እዚያ ቦታ ላይ ጆብ ማርኬቱ ሳቹሪትድ ይሆናል የምትለው አይደለም:: እምልህ If You have go to conserve every drop of rainfall, if You have to conserve soil የግድ የሰለጠነ ሰው ያስፈልገናል:: ይህ ደሞ መንግስት ከያዛቸው ፖሊሲዎች መካከል አንዱ ነው:: ለምሳሌ ይሄ TVT ማለት ቴክኒካል እና ቮኬሽናል ኢዱኬሽን ውስጥ ተካተዋል እና የስራ እድሉ አለ ባይ ነኝ :: of course, dominant employer will be the government, dominant employer will be the NGOs እሱ ብዙም የሚቸግረን ነገር አይደለም The problem is still there, ministries are there, ትልቁ ችግር የስራው volume ላይ ነው ኢትዮጵያ ትልቅ ሐገር ናት እና እነዚህ ሁለት ሶስት ተቋማት ጆብ ኦፖርቹኒውቲውን ሳቹሪት ያደርጉታል የሚል ግምት የለኝም::

**ራዕይ :-** የዲፓርትመቱ ስም በየጊዜው መለዋወጡ በተማሪው ሞራል ላይ የሚፈጥረው ስሜት አይኖርም?

**ዶ/ር ጠና:-** Disappointed ሊያደርግ የሚችል ነገር ሊኖር ይችላል:: ይህ ኘሮግራም ፍሌክሲብል መሆኑ ጥሩ ነው:: ሪጅድ ያለመሆኑ የሚሻል ይመስለኛል:: እንደዚህ ከሆነ ደግሞ more revise እናደርገዋለን:: መጀመሪያ ላይ ካሪኩለሙ ሲቀረጽ ላንድ ሪሶርስ ላይ ቤግ ወይሆነ ኤርያ ላይ ነበር ያተኮረው:: ውስጡን ስንፈትሸው ግን ትኩረት የምናደርግባቸው ጉዳዮች አሉ:: ለምሣሌ Irrigation, soil and water conservation በእነዚህ ኤርያዎች ላይ ብትወጡ ጠንካራ ኮምፒታንት መሆን ትችላላችሁ:: ኘሮግራሙ ፍሉድ መሆኑን መጥፎ አይደለም::

**ራዕይ:-** ትክክለኛ ወይም ወደ ፊት ሊፀና የሚችለው ስም የትኛው ነው?

**ዶ/ር ጠና:-** የኔ ፍላጎት ምንድነው . . . በተቻለ መጠን የኘሮግራሙ ስም clear ሆኖ ጥሩ ገፅታ እንዲኖረው ነው:: ቀደም ብሉ Soil and water engineering and Mgmt ብለን ሰይመነው ነበር ይህንንም ለሴኔቱ ማለትም ለዩኒቨርስቲው የበላይ አካላት አቅርበን እንደ የተሰጠን አሳይመት አለ:: ይኸውም Soil and water Engineering and Mgmt ስትሉት A kind of confusion ነው የሚፈጥረው ወደ ማኔጅመንቱ የሚሄድ ከሆነ ወደ ሰይል ሳይንሱ ነው የሚሄደው:: ወደ ኢንጅነሪንጉ የሚሄድ ከሆነ ቼክ አድርጉትና International Market ላይ የትኛው ነው ተቀባይነት ያለው ? በዚህ ጥያቄ ላይ ለዲኑና ለኔ አሳይመንት ተሰጥቶን ነበር:: እኔም ኢንተርኔት ብሮውዝ አድርጌ ስማቸው Soil and water engineering እንጂ ማኔጅመንትን ያገናዘቡ አይደሉም እና ለሚቀጥለው ሴኔት ኘሮፖዝ የምናደርገው Soil and water engineering ተብሎ qualified እንዲደረግ ነው::

**ራዕይ :-** ተማሪዎቹን የምትመክሩቸው ነገር ካለ?

**ዶ/ር ጠና:-** በአብዛኛው እዚህ ዲፖርትመንት ውስጥ የሚገባው analytic የሆነ ተማሪ ነው:: ማትስና ፊዚክስ መስራት የሚችል ነው:: እና ከሌሎቹ አንፃር ሲታይ life in engineering is miserable ነው ማለት ይቻላል:: በጣም ከፍተኛ ቻሌንጂንግ አለ:: በዚህ ቻሌንጂንግ ውስጥ ያለፈ ተማሪ ደግሞ ሪዋርዱ ቀላል አይሆንም እና በርትቶ መስራት ያስፈልጋል::

**ራዕይ :-** እናመሰግናለሁ::

*LIFE IN ENGINEERING IS MISERABLE*

ከገጽ 22 የዞረ

ጋር በሽታውን ሁለታችን እንጨርሰዋለን እንጂ ወደ ሌላ አይሄድም ባይ ነኝ: ትልቁ ነገር ደም መመርመሩ ብቻ አይደለም የሰብኝም እያልክ መዝለል የሰብህም አሰብኝም እያልክ መበቀል የሰብህም ትልቁ ምርመራ የመተማመኛ መንስኤህ ነው:: አንተ እኔን ከወደድከኝ እኔም ከወደድኩህ በሽታው ሁለታችንም ላይ አለቀ ማለት እኮ ነው:: ወደ ሌላ አይሄድም የኖረባቸውም እኮ ይጋባሉ: ከተጋቡ ወደ ሌላ አይዛመትም:: እኛ ንፁህ ነን ማለት አንችልም ምክንያቱም ስላልተመረመርን ቢኖርብንም እኮ በሽታው እኛው ላይ ነው የሚያበቃው::

**ራዕይ:-** የቤት ልጅ በሚባለው ጉዳይ ላይ አንዳንድዎቹ ምንም የግብረ ስጋ ግንኙነት ሳይኖራቸው ግን የቫይረሱ ሰለባ የሚሆኑበት አጋጣሚ አለ:: በዚህ ጉዳይ ላይ ምን ትያለሽ?

**ወሰን :-** በጣም የሚያሳዝነኝ ነገር እሡ ነው:: በእውነቱ ላለቅስ ሁላ እገደዳለሁ:: ዘለህ ተብጠህ የምታመጣው እኮ ፈልገህ: ተብጠህና በሽታውን ብለህ ያመጣኸው ከሆነ It's ok ችግር የለውም እኮ! አትቆጭም እንዴት እንዳመጣኸው ታውቀዋለህ ቀሪ ሂወቴን እንዴት ልምራው ብለህ ታስባለህ እንጂ ብዙም አታዝንም: ኤች አይቪ ኤድስ እኮ ቤትህ ድረስ አንኳኩቶ ሲመጣ እኮ በጣም ነው የሚያሳዝነው:: ያ ነው እኮ ሞት ማለት ሄደህ የምትሞተው ሞት ቀላል ነገር ነው:: ጦርሜዳም ስትሄድ እኮ በዋንኛ ነት አሸንፋለሁ ብለህ ነው የምትወስ ነው:: እንደጦሩ ሁሉ ይህን በሽታ እኛ ካላሸነፍነው ከፍተኛ አደጋ ላይ እየጣለን ነው የሚገኘው:: በተለይ. . . በተለይ ትውልድ ይዳን በኛ ይብቃ ብለው የሚያስተምሩትን ወገኖቻችንን ልንሰማቸው ይገባናል:: አንተ እኮ ምን ያህል ተዝቆ የማያልቅ ሐብትና ንብረት ቢኖርህም ጤና ከሌለህ ሁሉም ነገር ከቱ ነው:: በእርግጥ ዘመኑ የውበት ነው: ዘመኑም አሳሳች ነው ግን ከሁሉም በላይ ራስን መጠበቅን የመሰለ ታላቅ ብልህነት የለም:: አንተ ትልቅ ሰው ነህ የምትባለው ራስህን መጠበቅ ስትችል ነው:: ዩኒቨርስቲ መጥተሽ ነበር:: ለመሆኑ ጊቢያችንን እንዴት አየሽው ?

**ወሰን :-** እንደአጋጣሚ ሆኖ ማታ ከስራ ወጥቼ ነው ያየሁት:: በጣም ሰፊ ነው: ሕንፃውም ሁሉም እየተስፋፋ ነው:: በአጠቃላይ ተማሪውም ሆነ የዩኒቨርስቲው ማህበረሰብ በጣም ጉብዞች መሆናቸውን ለመገመት ችያለሁ:: በተረፈ በቀን ሣየው እነግርሃለሁ::

**ራዕይ:-** የእናንተን ድርጅት በገንዘብ የሚያግዘው አካል ማነው?

**ወሰን :-** በአብዛኛው ከማዘጋጃ ቤቶች ጋር በመተባበር ነው የምንሰራው ያው የጋራ ስራ ነው ማለት ነው::

**ራዕይ:-** ትርፋችሁና ደሞዛችሁስ?

**ወሰን :-** የእኛ ትርፍና ደሞዝ ንፁህና ውብ አካባቢን ማየት ነው:: በጣም ሊታሰብበት የሚገባው ነገር ግን ህዝቡ ከጉናችን ሊሰለፍ ይገባዋል::

ወደ ገጽ 29 ዞሯል

# ድንግልና

ከገጽ 25 የዞረ

**በተረፈ ግን በገ ተፈ መቆሙ ዋናው ምክንያት ምን እንደሆን ለሁላችንም ግልጽ ነው:: በተቻለ መጠን ግን አላማው ቢተካከል ጥሩ ነው::**

*ራዕይ*: - እንዴት ዘመን ልትባይ ቻልሽ ትርጉም አለው እንዴ?

ዘመን ዘመን ብቻውን ትርጉም የለውም ዘመን ተፈራ ሲሆን ሴንስ የሚሰጠው ይሄ ማለት ደግሞ ጊዜው ተፈራ ማለት አይደለ? እኔ በተወለድኩበት ጊዜ አለም ለሁለት ተከፍላ በኒውክሌር መሳሪያ አንዱ አንዱን የሚያስፈራራበት፣ ሶሻሊዝምና እምፐሪያሊዝም የተባሉት ሁለት የተለያዩ አይዲዮሎጂ ውስጥ ያሉ መሪዎች እርስ በርሳቸው የተፋጠጡበት ጊዜ ስለነበረ በዚያው ዘመን ተፈራ የሚለውን ስያሜ ላገኝ ችያለው:: That's why I'm Zemen Tefera.

**ራዕይ:- በአብዛኛው በአሁን ሰዓት ወጣቱ በወሲብ ምህዋር ሲሽከረከር ነው የሚታየው እንዳንቺ አይነቷ መንፈስ ጠንካራ ወጣት ደሞ አላማና እራዕይሽ እስከ ሚሳካ መታቀብን መርጠሻል:: በዕርግጥ መታቀብ ይቻላል?**

**ዘመን :- እዎ በጣም ይቻላል :: እዚህ ጋር አንድ እንድታውቅልኝ የምፈልገው ነገር ቢኖር ወጣቱን አታፍቅር እያልኩት አይደለም ያለሁት ወጣትነት መጫወቻ ጊዜ ነው: ወጣትነት የማፍቀሪያ ጊዜ ነው::ፍቅረና ወሲብ ማለት በጣም የተራራቁ ነገሮች ናቸው:: ወጣቶች ተልቅ ትኩረት ሊሰጡ የሚገባው እዚህ ላይ ነው:: ዛሬ ወደድኩሽ ብሉ ነገ የወሲብ, ጥያቄ ማቅረብ ተገቢ አይደለም:: ፍቅር እራሱ ጊዜ ይጠይቃል:: ጓደኛ ይሆኑ: ይዋደዱ: ፍቅርን ትስጠው ፍቅር ይስጣት: ግን ከጋብቻ በፊት የሚደረግን ወሲብ መቅወም አለባቸው መታቀብ ደሞ ይኸው እኛ ችልን አይደለም እንዴ ስለዚህ ምንም የሚከብድ**

**ነገር የለም . . . መታቀብ ይቻላል::**

**ራዕይ:- ብሪትኒ ስፒርስ በድንግልናዋ ሁሉንም ያስደነቀች ወጣት ድምፃዊት ነች:: ከብሪትኒ ምን ተማርሽ?**

**ዘመን :- ታዋቂነት በራሱ ትልቅ ጉዳት አለው:: ግን ያንን ነገር ተቋቁማ ከጋብቻ በፊት ወሲብ ላለማድረግ የወሰደችው እርምጃ ታላቅና የሷን ጥልቅ የማሰብ ችሎታ ቁልጭ አድርጉ ያሣያል:: አሁን በጣም የሚያስገርመው በእኛ ህብረተሰብ ድንግልና ለዛውን እያጣ የመጣው አሁን ነው:: የተገላቢጦሽ ደግሞ በእነሱ እንደ አዲስ እየተስተዋለ ነው::**

**ራዕይ:- የጫት ሐገር ነው ተወልደሽ ያደግሽው: ስለጫት ምን አይነት አመለካከት አለሽ?**

**ዘመን :- እኔ ባልቅምም ጫት የሐረርጌ ፀባይ ነው ካልቸር ነው: አንድ ሰው ቃመ አልቃመ ነውር የለውም::**

**ራዕይ:- የምታመሰግኛቸው ሰዎች ካሉ?**

**ዘመን :- በመጀመሪያ እግዚአብሄርን ላመስግነው እወዳለሁ:: በመቀጠል**

**አባቴን ካፒቴን ተፈራ ፍሰሃን: እንደ እናት ሆኖ ላሳደጉኝ ሁለቱ እህቶቼ ለየትናየትና መላዬ: ሁለቱን አያቶቼን: ወንድሞቼን: የአለማያ ዩኒቨርስቲ ተማሪዎችንና መላውን የኢትዮጵያ ህዝብ ላመሰግን እወዳለሁ::**

# ውስጣዊ ውበትን...

ከገጽ 27 የዞረ

**ራዕይ፡-** የእናንተ ግቢ ምን ያህል ጽዳቱን የጠበቀ ነው?

**ወሰን :-** በእርግጥ የምታየውና የምትናገረው ነገር አንድ ስለማይሆን አሁን ኤግዛጅሬት አድርጌ ብነግርህ ላይዋጥልህ ይችላል:: ያው ግን አበባ አለ ደስ ይላል:: በተረፈ አዲስ አበባ ስትመጣ እጋብዝሃለሁ::

**ራዕይ፡-** ስለ ዛፍ ጥቅም የምትይው አለ?

**ወሰን :-** ይህ እኮ የታወቀ ነው ዛፍ በረሃማነትን ይከላከላል በተጨማሪም ውበት ነው:: በተለይ እዚህ ሐረር ሚት ይቃማል:: አንዲት ዛፍ ተክሉ እዛች ጥላ ስር ቢቀመጥ ምን ያህል ጥላው እንደሚያስውበው :

**ወሰን :-** በአለም አቀፍ ደረጃ የተቋቋመ ከተሞችን በመምረጥ የሚሸልም ድርጅት አለ:: ከኢትዮጵያም ካሉ ከተሞች መካከል ሐረር የሰላምና የመቻቻል ከተማ ተብላ ተሸልማለች:: በፀዳት በኩል ደሞ ይቀራታል:: እነዚህ ሁለቱ ሐሳቦች አይጋጩም?

**ወሰን :-** እኔ በበኩሌ በጣም ገርሞኛል:: ይህን ሁሉ ሽንትና ሰገራ ይዛ አዋርድ ስታገኝ ሹፈት እንጂ ሌላ አይመስለኝም:: ውይ! ሐረር ቆንጆ ናት ብለህ የምትሸፋፍነው ነገር አይደለም:: ለዚህ ሁሉ ችግር የሚያበቃን ደሞ መሸፋፈናችን ነው:: እና ግልጽ በግልጽ መወያየት አለብን:: እነደነገርኩህ ሐረር ሽንት አለ:: ሽንቱ ይጽዳ : ቆሻሻው ይጽዳ :: ያ ታይቶ ነው አዋርድ መሸለም ያለባት:: እንጂ ሠገራ አፍጥጦ እየታየ አዋርድ ቢሰጡህ እያሸፉ ለመሆናቸው ጥርጣሬ ሊገባህ አይችልም::

**ራዕይ፡-** ከጋሽ አበራ ባህርይ ውስጥ የሚመችሽ የትኛው ነው? የማይመችሽስ?

**ወሰን :-** የማይመቸኝ ብዬ የምልህ የለም እንደው ሰው አጋነንሽ አይበለኝ እንጂ ልነግርህ አልችልም በቃ ሁሉ ነገሩ ይመቸኛል ትዕግስቱን በጣም ነው የምወድለት:: እኔ ነኝ እንደውም ይህ ለምን ሆነ አልሆነ እያልኩ የምቆጣው ከሱ ትዕግስት እኔ ተማርኩኝ ነው የምለው:: እኔ አሁን ትንሽ ረጋ ብያለሁ ልጅነቱ ነበር ገንፈል የሚያደርገኝ አሁን ግን ትግስቱ ተጋብቶብኛል

**ራዕይ፡-** ለህዝቡ የምታስተላልፊው መልዕክት ካለ?

**ወሰን :-** አዎ የኔ ፍላጐትና ምኞት ሺ ጋሽ አበራ ሞላዎችን እንደችግኝ ማፍላት ነው::

**ራዕይ፡-** ባለቤትሽን ምን የህል ትወጂዋለሽ?

**ወሰን :-** በጣም ትዕግስተኛ ጨዋና ሰው የማያስቀይም በመሆኑ እኔ በጣም ነው የምወደው::

**ራዕይ፡-** ከስራችሁ ጋር በተያያዘ ያገኛችሁት ሽልማት ይኖር ይሆን?

**ወሰን :-** አዎ በአካባቢ ልማትና ውበት ምክንያት ለንደን ላይ በተደረገው አዋርድ የወርቅ ተሸላሚ ለመሆን ችለናል:: በዚህ ውድድር የአዲስ አበባ ማዘጋጃ ቤት ሁለተኛ ነበር የወጣው::

**ራዕይ፡-** ቁመትሽ ስንት ነው?

**ወሰን :-** አንድ ሜትር ከ62 ወይም ከ63 ነው ከሁለት አንዱ ውስጥ ነኝ::

**ራዕይ፡-** ቅርጫት ኳስ ትጫወቻለሽ ማለት ነው?

ወደ ገጽ 32 ዞሯል

# አስትሮሎጂ



Shelly von Strunckel,



**ARIES (MARCH 20 – APRIL 18)**
Naturally you wouldn't want to leave your decisions to others. Yet you're uncharacteristically unsure as you have numerous options to consider. Let those concerned know what interests you, but continue to explore existing options and those that are likely to arise this week.



**TAURUS (APRIL 19 – MAY 19)**
You're still feeling upset about situations where you were cornered into making decisions. Now justice comes, in the form of certain individuals who can, and will, insist that these wrongs be put right. Allow them to take the lead and things should go surprisingly smoothly.



**GEMINI (MAY 20 – JUNE 20)**
One of your greatest gifts as a Gemini is your agile mind meaning you can come up with all sorts of solutions to even the toughest of dilemmas, as is the case with certain joint ventures. Admirable as your ideas are, remember that what you arrange must take finances into account.



**CANCER (JUNE 21 – JULY 21)**
Partners at home or at work may have declared their views, making it clear that there was no chance they'd change their way of thinking. However, they couldn't possibly have anticipated recent developments, which have them viewing things from a completely different perspective.



**LEO (JULY 22 – AUGUST 22)**
Having discussed dividing responsibilities, you thought things were settled. Now a completely new approach requires starting from square one. Tedious. But try keeping things same and it will soon become clear that you're doing no more than creating complications for yourself.



**VIRGO (AUGUST 23 – SEPTEMBER 21)**
Don't think that because some people care about you, they'll also know what will make you happy. Obvious as these things are to you, they're far more of a mystery to them than you think. At least give them hints, although simply saying what you want would be best.



**LIBRA (SEPTEMBER 22 – OCTOBER 22)**
For ages you've been trying to convince family members that changes are wise, but with little success. Now suddenly they're keen to reorganise. But what's irritating is they're insisting the plans you've been suggesting are their own. Don't argue. At least, they're willing to cooperate.



**SCORPIO (OCTOBER 23 – NOVEMBER 21)**
While you'd never encourage anybody to argue unnecessarily, you suspect it's not until some people are upset will they reveal true feelings. That's probably is the case. It's true provoking them to get facts may be a risky strategy. But it also may be your only choice.



**SAGITTARIUS (NOVEMBER 22 – DECEMBER 20)**
At the time you made arrangements, you didn't realise you were overcommitting yourself. Now that it's clear you have, sooner you rearrange things, the better. This may mean backing out of certain plans you were looking forward to. But it's better than rushing through them.



**CAPRICORN (DECEMBER 21 – JANUARY 18)**
If you're feeling concerned about highly personal issues, it's no surprise. In fact, because the recent Capricorn New Moon raised many questions about personal and future plans, you've been questioning various elements of your life that, ordinarily, you wouldn't have given a thought to.



**AQUARIUS (JANUARY 19 – FEBRUARY 17)**
Everybody's busily making plans. While you know the general direction in which you'd like to go, nothing excites you enough. Take it slowly. While you may not be sure what you want to do until early February's Aquarius New Moon, once you do, it will have been worth the wait.



**PISCES (FEBRUARY 18 – MARCH 19)**
Having realised it's better to alter plans, you're now worried of how those changes would influence others. Answer is, they'd have a tremendous influence, and while they won't thank you now, eventually they will, once they learn what you prevented them from doing.

**IF IT'S YOUR BIRTHDAY**
Last thing you want to do is make changes you'd regret. Yet, you can't ignore the restlessness you've been feeling. This isn't just about escaping, but broadening your horizon. Explore your ideas and whatever arises. With what you learn and those you meet, you won't regret it.

አስትሮሎጂ

# ብርክት ተረፈ እንኳን ደስ ያለሽ



ብርክት በማእረግ ድግሪዋን ስትቀበል

ከግራ ወደ ቀኝ(ግርማ ዋቄ የኢትዮጵያ አየር መንገድ ዋናስራ አስኪያጅ ፕሮፌሰር በላይ ከሳ ና ደ/ር ጠና አላምረው)

ብርክት ተረፈ በአለማያ ዩኒቨርስቲ በርከታ እንቅስቃሴዎችን ስታደርግ የቆየች ለሌሎችም አርአያ ለመሆን የበቃች ወጣት ነች፡፡የዩኒቨርሲቲው ጸረ-እድስ ንቅናቄ ጸሐፊና የገርልስ ክለብ መስራችና ሰብሳቢ በመሆን ታላቅ ጀብዱ የሰራች ብርቅዬና ድንቅ ልጅ ነች ፡፡የራእይ መጽሄት ዝግጅት ክፍልም መልካም የስራ ዘመን እንድገጥምሽ ይመኛል፡፡

ከገጽ 29 የዞረ

**ወሰን** :- (ሳቅ) በምን ቁመቴ?!

**ራዕይ:-** የፍቅር ደብዳቤ ጽፈሽ ወይም ተጽፎልሽ የውቃል?

**ወሰን** :- እኔ እንኳን እንደዚህ አይነት ነገር ላይ አልደረስኩም ነበር:: ማለት በ1992ዓ.ም እንዳልኩህ የ18 ዓመት ልጅ ነበርኩኝ ግን ትዝ ይለኛል አንድ ልጅ እወድሻለሁ ብሎ በ50 ሉክ ደብተር ላይ ጽፎና ስዕል ሁሉ ስሎ ሰጥቶኝ ነበር:: even ለትንግርት ቤቴ አስተምጪዋለሁ እኔ ግን የፍቅር ደብዳቤ ምናምን እኪሌ ወድጀህ ብዬ ጽፌ አላውቅም::

**ራዕይ:-** በልጅነት ትመኚው የነበረው ሙያ ወይም ኘሮፌሽን ምን ነበረ?

**ወሰን** :- እኔ እመኘው የነበረው ታይኘ መምታትን ነበር:: ምክንያቱም ሲስተር ስትመታ ስለነበር እሡ ነበር ምኞቴ ግን እንደ አጋጣሚ ሆኖይኸው እዚህ ኘሮጀክት ውስጥ ነኝ:: ይኸ ደሞ የሁለታችንም ነዉ:: ምክንያቱም እኔና እሡ already አንድ ሆነናል:: ይሁን እንጂ ከልጅነቴጀምሮ የሰው ጥገኛ መሆንን አልሻም ነበር:: ለምን ቀሉ ሸጩ አላድርም: ከሰው መጠበቅ አልወድም ነበር::

**ራዕይ:-** በኘሮጀክቱ ውስጥ ያገኙ ሚና ምንድነው?

**ወሰን** :- የአዲስ አበባው ኘሮጀክት ላይ በነበርኩበት ሰዓት እማር ነበር ከኤሌክትሪክሲቲ በተጨማሪም በኤዲቲንግና በቪዲዮ ግራፊ ኮርስ ተመርቂያለሁ:: በዚህም ሙያ የሚሠሩትን ስራዎች ከስር ከስር ቪዲዮ እቀርፃለሁ:: በተጨማሪም ሰራተኞቹን ማሰራትና ከሠራተኞቹ ጋር መስራት የኔው ድርሻ ነው::

**ራዕይ:-** ሙሉ ስምሽ ማን ይባላል?

**ወሰን** :- ወሰን ብርሃኑ ምህረት::

**ራዕይ:-** ለዩኒቨርስቲ ተማሪዎች ያለሽ መልዕክት ቢገለጽ?

**ወሰን** :- አገር የምትኖረው ወጣት ሲኖር ነው:: ወጣቱ ደግሞ በቴክኖሎጂ ናዳ ሳቢያ በኤች አይቪና በሌሎች ችግሮች ፍዳውን እያየ ነው:: የዩኒቨርስቲ ተማሪዎች ደሞ ከ14ቱም ክፍለ ሐገር የተውጣጣችሁ ስለሆነ ዛሬ ተምራችሁ ለነገ ሐገራችሁ አለኝታ ና ቤዛ ልትሆኑ የምትችሉት ብልጭልጩ ሁሉ ሳያታልላችሁ ለፍታችሁ ጥራችሁ ግራችሁ ወርቁ ላይ መድረስ ስትችሉ ነዉ:: በተረፈ ለህይወታችሁ ዋጋ ስጡ::

**ራዕይ:-** አመሰግናለሁ::

_____//_____

## <u>ቁማር</u>

*ጉና ከድር*
*ያኔ ከጥንቱ*
*ጽድቅና ሐጢያት*
*ቁማር ሲጫወቱ*
*እንደ እድል ሆኖ*
*እንደ ዕጣ*
*ጽድቅ እያሸነፈ*
*ሂወትን ሲያወጣ*
*ሃጢያት መዘዘኛው*
*በሽንፈት ተናዶ*
*እሳት የላሰ ልጅ*
*ኤች አይ ቪን ወልዶ*
*ይኸዋ ሲጫወት*
*ዘውድ ጉፈር ሲገፉ*
*ሞት ብቻ ያወጣል*
*ሂወት እየደፋ::*

*(ደንበል ደስታ)*

የዓለማያ ዩኒቨርሲቲ ፀረ-ኤድስ ንቅናቄ ለ1997 ዓ.ምተመራቂዎች በሙሉ እንኳን ደስ አላችሁ እያለ መልካም ምኞቱን ይገልጻል:: በተመረቃችሁበት የትምህርት ዓይነት ሀገራችሁን ለማገልገል ትችሉ ዘንድ ከምንም በላይ ለሕይወታችሁ ዋጋ ስጡ::

# የዓለማያ ዩኒቨርሲቲ ፀረ-ኤድስ ንቅናቄ

# እንኳን ደስ አላችሁ



Endashaw Girma
( Former Tresurer )



Sintayehu Aregahagn
( Print Head )
( ትንሽ የተስፋ ፍሬ ... )



Mulu Debela
( AUAAM- Member )

«ሺ አራት መቶ ቀን(4 ዓመት)
በአንድ ቀን
ምረርቃት ተጠናቀቀ::»አይገርምም!!

# CONGRATULATION



SISAY TESFAYE
(Executive)

ስትስቅ ስትጫወት
ሁሉም ያምርብሃል
ስቀልድ ስቴምነገር
አስቦ ፈጥሮኃል
ታዲያ በወድህም ከልቤ አምርሬ
ስምቻለሁ ወሬ
ልትለየኝ ዛሬ
ልትሄድ ልትመረቅ
· ትልቅ ሰው ልትሆን
በስራ አገርን
ትውልድን ልታድን
ስትሄድ እርቀህ
ከኔ ወዲያ ማዶ
ትዝታህ አለልኝ
አይደለሁም ባዶ::
/ከእመቤት ወርቅነህ/
( ለ1997 ዓ.ም ተመራቂ ወንዶች በሙሉ )

## ፎቶ ባቴ

እጅግ በጣም ጥራት ያላቸውን ፎቶዎች በማንሳት የሚታወቀው ፎቶ ባቴ ለመላውተመራቂዎችእንከዋን ደስ አላችሁ መልከም ምኞቱን ይገልጻል::

ፎቶ ባቴ ምንጊዜም ተመራጭ ነው::

# ሚዲያ

## መጨረሻውን ባናውቅም አጀማመሩ ግን እጅግ ያማረ ፕሮግራም "ኢትዮጵያን አይድልስ"

በለኮመልዛ ቱጄይ

አሁን ያለንበት ክፍለ ዘመን ከየትኛውም ጉዳይ ለበለጠ ሁኔታ ለመዝናኛው ኢንዱስትሪ ከፍተኛልማት ለመስጠቱ ቅንጣት ታህል ጥርጣሬ ሊያድርብን አይገባም :: ምክንያቱም ዕውነታው በገሃድ የሚታይ ከመሆኑም በላይ ማንኛውም የህብረተሰብ ክፍል ትኩረቱ ወደዚሁ በመሆኑ ሌላ ማስረጃ መጥቀሱ ያን ያህል አስፈላጊ አይደለም ::

በተለይም የፊልሙ ኢንዱስትሪ በከፍተኛ ሁኔታእያንሰራራ የሚገኝና በርካታ አፍቃሪያንን ለመሣብና ለመማረክ የበቃ የመዝናኛ ክፍል ነው ለምሳሌ ያህል አንጋፋዎቹ የአሜሪካን የፊልም ኩባንያዎች እይታ የሚያበቋቸው ፊልሞች ሁልጊዜ ለኦስካርና ለሌሎችም ሽልማት ከመታጨት እስከማሸነፍ መድረሳቸው :: በዚሁ የኢንዱስትሪ ዘርፍ የግል ባለሀብቱ ምን ያህል እንደታሰበና ትርፋማ እንደሆነ ቁልጭ አድርጎ ያሣያል ::በሆሊውድ መንደር ስማቸው ከገነነ የዘርፉ ኩባንያዎች መካከል ሆሊውድ ፣ ኮሎምቢያ፣ ፒክቸርስ ፣ H 20 Century Fox ዋርነር ብሮስና ሌሎችም ይገኙበታል ከአሜሪካን ወጣ ስንልም የጥራት ነገር ብዙዎችን ቢያወዛግብም ብዙ ፊልሞችን ለእይታ ለማብቃት የኢንዱስትሪውሆሊውድ ተጠቃሽ ነው ::

ከፊልሙ ባሻገር በመዝናኛው ኢንዱስትሪ ውስጥ ዘልቀው በመግባት ስማቸውን ለመትከልየበቁ ታላላቅ የቴሌቭዥን ኩባንያዎችም አሉ :: ከእነዚህ መካከል በመላው ዓለም የሚገኙ በብዙ ሚሊዮን የሚቆጠሩ ተመልካቾችን ለመሣብ የበቃው አንጋፋው POSTU አገልግሎት ነው ::

ይህ የቴሌቭዥን ካምፓኒ ከትንሿ የካርቱን ፊልም እስከ ትልልቆቹ አክሽኖችና አድቨንቸር ፣ ትሪሊርና ሮማንስ ታሪኮችን ላየር በማብቃት ትርፍም ዝናም ማጋበስ ከጀመረ ውሎ አድሯል ::

በዚህ POSTU አገልግሎት በጣም በርካታ ቻናሎች ከመካተታቸው የተነሳ ተመልካች ባብዛኛው የሚደበርበት አጋጣሚ በተዓምር ካልሆነ በስተቀር አይፈጠርም :: ምክንያቱም ቢፈልግ ቶክሾው ቢያስፈልገው ሙዚቃ ቢፈልግ ስፖርት ብቻ የሌላ የለም ማለት ይቻላል ::

ይህ የሚያመለክተው ከሌላው ይልቅ የመዝናኛው ኢንዱስትሪ በምን ያህል ፍጥነት ወደፊት እየተከተለ ከመሆኑን ነው :: ይሁን እንጂ ይህ ሁሉ የሚሆነው ለውጭው ዓለም ነው ::

በሐገራችን ያለው ተጨባጭ ሁኔታስ ምን ይመስላል ምንም እንኳን ሐገራችን ኢትዮጵያ በዚህ ዘርፍ ገና ዳዴ እያለች ቢሆንም አሁን አሁን እየታዩ ያሉት ክስተቶች ግን ተስፋን ፈንጣቂ ሆነው አግኝቼዋለሁ:: በአሁኑ ሰዓት በርካታ ፊልሞች ለዕይታ እየበቁ ነው ሲኒማ ቤቶችም እየተገነቡ ነው ባጠቃላይ ከአውደ አንድ እየተሸጋገርን ነው ማለት ይቻላል::

የቴሌቪዥን ሥርጭታችንና የሬዲዮ ሽፋናችን ግን ከድህነታችን ጋር ተደማምሮ ነው መሰለኝ ገና አልተንቀሳቀስንም ማለት ይቻላል ለ70 ሚሊዮን ህዝብ አንድ ቴሌቭዥን እና አንድ ሬዲዮ በቂ ነው ብሎ የሚከራከረኝ ሰው ያለ አይመስለኝም እንደዝያውም ሆኖ የኢትዮጵያ ቴሌቭዥን ራሱን ለማደስ እያደረገ ያለው ጥረት ይበል የሚያሰኝ ነው :: በብዛኛው ስኬትን ባይጎናፀፍም *TU African* መዝጋቱ አግባብነት ባይኖረውም *ETV- Music* መከፈቱ ታላቅ እምርታ ነው :: 120 ፕሮግራም ለማሻሻል የተደረገው ጥረትም ጥሩ ነበር የአለቤየቶክ ሾው ፕሮግራም እንዲሁ አሁን ደግሞ እውነትም ኢቲቪ 1ሳይሆን 10 እርምጃ ወደፊት ተራምዷል የሚያሰኘውን የኢትዮጵያን ኢይድልስ ከጀአቲ ሚዲያና ኢንተርቴይመንት ጋር መጀመሩ ሆድ የባሰውን ተመልካች እንጀት ሊያርስ ቆርጦ ተነስቷል ማለት ይቻላል ::

**ከ 2003 እስከ ሐምሌ 2005 ድረስ ያለውን የሰልፍ ሄልፕ አለማያ-II የተቀናጀ የገጠር ልማት ፕሮጀክት እንቅስቃሴ**

## የሰብል ልማትና የእንስሳት እርባታ

በሰብል ምርት ዙሪያ የሚሰራው ስራ ፕሮጀክቱ ከሚያከናውናቸው ወደ ስምንት የሚጠጉ አበይት ሥራዎች ውስጥ አንዱ እንደመሆኑ መጠን በስሩ የተለያዩ አይነት ተግባራትን አቅፏል:: እነዚህም የምርጥ ዘር ማሰራጨት፣ የፀረ ተባይ መድሀኒትና ለዚህ የሚያስፈልገው የመርጫ መሳሪያ ሥርጭት አጋዥ ተክኖሎጊዎችን ማስተዋወቅ፣ ገበሬዎችን በመስኖ ዙሪያ አደራጅቶ ማገዝ እንዲሁም በገበሬዎች ማሳ ላይ የሚደረገው የዘር ማባዛት ሥራ ይገኙበታል:: በዚህ መሰረት እስከአሁን ላለው ጊዜ 961.42 ኩንታል የተሸሻሉ የማሽላ፣ የበቆሎ፣ የቦሎቄና የለውዝ ዘሮችን ባማሰራጨት 14190 ገበሬዎችን ተጠቃሚ አድርጓል::



**Sorghum Field-Improved Muyra**

እንዲሁም 720.58 ኩንታል የድንችና የስከር ድንች 3401 ኪ.ግ የነጭና የቀይ ሽንኩርት እንዲሁም 119.65 ኪ.ግ የተለያዩ አይነት የአትክልት ዘሮችን በማሰራጨት በአጠቃላይ 2534 ገበሬዎችን አሳትፏል:: አጋዥ የሆኑ ተክኖሎጂዎችንም ለማስተዋወቅ ባደረገው እንቅስቃሴ 5 የድንች ዘር ማከማቻ መጋዘኖችን (DLS) በተለያዩ ቦታዎች ላይ በማሰራት በአከባቢው የሚገኙትን ገበሬዎች ተጠቃሚ አድርጓል:: ከዚህም በተጨማሪ በድምሩ 39 ያህል አባላትን የያዘውን ሦስት የመስኖ ቡድን በማደራጀት አራት የውሃ መሳቢያ ሞተሮችን ሰጥቷል:: የተሰራጩትንም የምርጥ ዘር በአከባቢው ለማሰራፀ በ 819 ገበሬዎች ላይ የምርጥ ዘር ማባዛት በማከናወን ከተጨማሪ ዋጋ እንዲጠቀሙ አድርጓል::

በእንስሳት እርባታ ዘርፍም ለገበሬዎች ጠቃሚ የሆኑ የተለያዩ አይነት ተግባራትን ያከናወነ ሲሆን የተሸሻሉ ዶሮዎች ስርጭት፣ ለከብት ማዳቀል ስራ እገዛ ማድረግ፣ የእንስሳት ክሊኒኮችን መገንባት በዋነኛነት ይጠቀሳሉ:: እስከሁንም ባለው እንቅስቃሴም ከ 1445 የተሻሻሉ ዶሮዎች በማሰራጨት 210 ሴቶች ያሳተፈ ሲሆን የእንስሳት ክሊኒክ በማስገንባት በአከባቢው ያለውን የእንስሳት ህክምና እጥረት ቀርፏል:: በተጨማሪም 33 ማእከሎች ላይ የሚደረገውን የከብት ማዳቀል ስራ ድጋፍ ያደረገ ሲሆን በነዚህ ቦታዎች 6 ክራሾችን አሰርቷል:: ዱሃ ሴቶችን መደገፍ አላማ ባደረገው ስርጭትም 86 ፍየሎችን ለ 43 ሴቶች በማከፋፈል እገዛ አድርጓል::



Vetrinary service

## የአፈርና ዉሃ ጥበቃ

አለማያ-II የተቀናጀ የገጠር ልማት ፕሮጀክት የምግብ ዋስትናን በቀጣይነት ለማረጋገጥ የተለያዩ የአከባቢ ጥነቃ ስራዎችን እየሰራ ይገኛል:: ፕሮጀክቱ በማስፋፋት ላይ ያለውን የመሬት መራቆትን ግምት ውስጥ በማስገባት በቂ በጀት መድቦ እንደየ አከባቢው ሁኔታ የችግር መጠን ከአለማያ ወረዳ የገጠር ልማት ጽ/ቤት ጋር በጋራ በመሆን ውጤታማ ስራዎችን አስመስግቧል::



Soil & Water conservation - Gully treatment

በመሆኑም ባለፉት ሦስት ዓመታት 60 የግለሰቦች ችግኝ ጣቢያ በመቋቋም ገበሬዎቹ በአከባቢያቸው ቀጣይነት ባለው መልኩ ችግኞችን እንዲያገኙ ከመረዳቱም ባሻገር ተጨማሪ የገቢ ማመንጫ ሆኖላቸዋል::

በተጨማሪም በ 6 የገበሬ ት/ቤቶች ችግኝ ጣቢያዎችን በማቋቋም ለተማሪዎችና ለት/ቤቱ ማህበረሰብ የችግኝ አፈላልና አጠቃቀም ግንዛቤን አዳብሯል::

ከዚህም ባሻገር የአንባቢውን የደን መመናመን ግንዛቤ ውስጥ በማስገባትና በቂ ችግኞችን አፍልተው ለገበሬው ለማዳረስ ይረዳ ዘንድ 3 ማእከላዊ ችግኝ ጣቢያዎችን አቋቁሟል::

ከነዚህ ችግኝ ጣቢያዎች 1,112,350 የዛፍና የፍራፍሬ ችግኞች አፍልተው ከ600 በላይ ለሚሆኑ ገበሬዎች አሰራጭተዋል::

የፊዚከል ሥራዎች (Physical measures) በተመለከተ ፕሮጀክቱ እስከ 2005 ድረስ 7.5 ኪ.ሜ የበረበር ቁጥጥር፣ 52.5 ኪ.ሜ በእርሻ መሬት ላይ እርከን የማሰራት እንዲሁም 40000 የግማሽ ጨረቃ (Micro-basin) እና የተፈጥሮ ሀብታቸው በታራቆቱ መሬቶች ላይ ሰርቷል::

የዝናብ ማነስና ያለወቅቱ ማቋረጥን ግምት ውስጥ በማስገባት 72 የውሀ ማቆሪያ ገንዳዎችን በመስራትና በመጠቀም 72 ገበሬዎች ውሀን አሰባስቦ ከ3.6 ሄክታር

በላይ የሚበልጥ መሬት እንዲያለሙ ተደርጓል::

በአጠቃላ የአፈርና ውሀ ጥበቃ ሥራዎችን ፕሮጀክቱ ትኩረት ሰጥቶ በመስራቱ ገበሬዎች በአጥጋቢ የአከባቢ ጥበቃ ግንዛቤን ከማግኘታቸው ባሻገር ለወረዳው ጥሩ የማስተማሪያ ቦታ (Demonstration site) ሆኗል::

# ትምህርት

በፕሮጀክቱ ትኩረት ከሚሰጣቸው የልማት ስራዎች አንዱ ትምህርት ነው:: አላማውም የትምህርት ሽፋንን በወረዳው ማስፋትና ለትምህርት ጥራት የበኩሉን አስተዋፅኦ ማድረግ ነው:: በዚሁም መሰረት እንደሌላው የፕሮጀክቱ ስራዎች ለትምህርት የሚደረጉ ድጋፎችን ከወረዳው የትምህርት ቢሮ ጋር በመሆን ያከናውናል:: ፕሮጀክቱ ድጋፍ ከሚያደርግናቸው መስኮችም የአንደኛ ደረጃ ት/ቤት ግንዳታ፣ በት/ቤት ውስጥ ለሚገኙ ክበባትን ድጋፍ፣ የመሰረተ ትምህርት ድጋፍና የተማሪዎች መቀመጫ ድጋፍ ናቸው:: በዚሁ መሰረት 2 የአንደኛ ደረጃ ት/ቤት ግንባታ፣ ለ38 ክበቦች ድጋፍ፣ ለ16 የመሰረተ ትምህርት ማእከላት እንዲሁም ለአራት ት/ቤቶች 120 የተማሪ መቀመጫዎች ድጋፍ አድርጓል::

## የሴቶች ፕሮግራም

የዚህ የስራ ክፍል አላማ የሴቶችን ኢኮኖሚያዊ፣ ማህበራዊ፣ ፖለቲካዊ አቅም ማሳደግና በማናቸውም የልማት ስራ ውስጥ ከወንዶች እኩል ተሳትፎ እንዲሁም ተጠቃሚ እንዲሆኑ ማስቻል ነው::



Sheep fattening –Women's income generation

በሰልፍ ሄልፕ አለማያ-II የተቀናጀ የገጠር ልማት ፕሮጀክት ውስጥ ከላይ የተጠቀሱትን አላማዎች ከግብ ለማድረስ የሚያስችሉ ስራዎችን በማከናወን ላይ ይገኛል:: ከነዚህም ውስጥ ሴቶችን በቁጠባና ብድር ህብረት ስራ ማህበራት በማደራጀትና ለብድር አገልግሎት የሚውል ብር (Grant fund) በመስጠት የሴቶችን ገቢ ለማሳደግ የሚያስችል ግብዐቶችን እያቀረበ ይገኛል::

ሴቶች የቤተሰብ ተንከባካቢ በመሆናቸው የቤት ውስጥ ስራዎችን ለማቃለል የሚያስችሉ ስልጠናዎች እንዲያገኙ ተደርጓል:: ከነዚህም ሌላ የተለያዩ የገቢ ማስገኛዎችን፣ የቤተሰብ ምጣኔ፣ በጎጂ ባህሉ በስርአተ ፆታ ጉዳዬች ላይ የሚያተኩሩ የግንዛቤ ማስጨበጫ ስልጠናዎች በተለይ ለገጠር ሴቶች በመስጠት ላይ ይገኛል::

ከላይ በተጠቀሱት የስልጠና አይነቶች 596 ሴቶችን አሰልጥኗል:: ሦስት የቁጠባና ብድር ህብረት ስራ ማህበራት በማቋቋም 305 ሴቶችን በማደራጀት የብድርና ቁጠባ አገልግሎት ተጠቃሚ እንዲሆኑ አስችሏል:: ፕሮጀክቱ 171 ሴቶችን በልዩ የገቢ ማመንጫ ፕሮግራም ለማሳተፍ የዶሮ፣ የፍየልና የተለያ ያትክልት ዘሮችን በግብአትነት አቅርባል::

ባጠቃላይ ፕሮጀክቱ የሴቶችን መሰረታዊ ችግሮች የሚዳስሱ ተግባራትን ከላይ በተጠቀሰው መልኩ በማከናወን ላይ ሲሆን

በቀጣይም በአሰራሩ ላይ መጠነኛ ለውጥ በማድረግ ሴቶችን ስልታዊ ፍላጎት በሚዳስስ መልኩ ለመስራት የስርአተ ፆታን ጉዳዩን በሁሉም የልማት ስራ ውስጥ በማካተት (Gender mainstreaming) ለማስራት ጀምር እንቅስቃሴዎች እየተደረጉ ናቸው::

## የመጠጥ ውሀ

ፕሮጀክቱ ንጹህ የመጠጥ ውሀን ለህብረተሰቡ ለማዳረስ ባለው አላማ 16 በእጅ የሚሰሩ ጉድጓዶችን በማስቆፈር ከ1200 በላይ ቤተሰቦች ተጠቃሚ ሆነዋል::ከዚህም በተጨማሪ 3 የምንጭ ማጎልበት ሥራዎችን ሰርቶ ከ7500 በላይ ለሆኑ ሰዎች ንጹህ የመጠጥ ውሀ ተጠቃሚ ሲሆኑ፣ በቆላማ ቀ/ገ/ማህበራት ውስጥ 7 በማሽን የሚቆፈሩ የውሃ ጉድጓዶችን ለማስገንባት ለኮንትራክተር ሰቶ እያሰራ ይገኛል::



## አቅም ግንባታ

በዚህ ስር ፕሮጀክቱ በስልጠናዎችንና የተለያዩ አይት ድጋፍችን ያከናውናል:: በዚህ መሰረት እስከሁን ባሉት ጊዜያቶች ለ1003 ገበሬዎችና ለ107 የተለያዩ መስሪያ ቤቶች ሰራተኞች እንዲሁም ለ264 ሴቶች ስልጠናን አቀናጅቷል:: እነዚህም ስልጠናዎች ባለው ሁኔታና በስልጣኞች ፍላጎት ላይ የተሞረከዘ ሲሆን ይህም ያላቸውን ፍላጎት ለመቀየር አነሳስቷል:: ከዚህ በተጨማሪ በወረዳው ውስጥ ላሉት የመ/ቤቶች ኮምፒውተሮች፣ ፎቶ ኮፒ መሽንና ሌሎች የቢሮ እቃዎችን እንዲሁም በሞተር ሳይክል ጥገና ድጋፍ በማድረግ በነዚህ ዙሪያዎች ያለውን ክፍተት ሞልቷል:: የወረዳውም በስብሰባ አዳራሽ ችግር ለመቅረፍ ባደረገው እንቅስራሴ እንድ የስብሰባ አዳራሽ አስገንብቶ አስረክቧል:: ከአለማያ ዩኒቨርስቲ ጋር ባለው የስራ ግንኙነትም የግብርና ስርፀት ተማሪዎችን በሚሰሩት የመስክ ልምምድ ድጋፍ ይሰጣል:: በዚህም ድጋፍ የተመረቁና አሁንም በመማር ላይ ያሉ 279 ተማሪዎች ተጠቃሚ ሆነዋል::

## የህብረተሰብ ጤና

ፕሮጀክቱ በህብረተሰብ ጤና በኩል በርካታ ሰዎችን ለወረዳው ህብረተሰብ በመስራት ላይ ሲሆን በዋነኛ ነት ከተሰሩት ውስጥ 100 የልምድ አዋላጅ፣ 30 ህብረተሰብ አቀፍ፣ የቤተሰብ ምጣነ ሰጪ እንዲሁም 100 የወባ የመንደር ሰራተኞችን በማሰልጠን ወደ ስራ እንዲገቡ አድርጓል::

እንዲሁም የጤና ሽፋን ለማሰደግ 1 ጤና ኬላ ተሰርቶ ስራ የጀመረ ሲሆን 1 ደግሞ በመሰራት ላይ ይገኛል። ለዚህም ጤና ኬላ እና ለሁሉም የጤና ድርጅት የመድኃኒት አቅርቦት እንዲጨመር ሲባል ለ2 ጤና ኬላ የልዩ መድኃኒት ቤት በኩል የብር ድጎማ ተደርጓል። በሌላ በኩል ደግሞ የአከባቢ ጤና ለማጠናከር ሲባል 5 የህዝብ ሽንት ቤትና 200 የሽንት ቤት ክዳን በመስራት ለህዝቡ አከፋፍሏል። እንዲሁም የወረርሽን በሽታ ለመቆጣጠረው የብር ድጎማ ለመድኃኒት መግዢ ለውሎ አበልና ለነዳጅ የሚሆን ለወረዳው ጤና ጥበቃ ጽ/ቤት ድጋፍ ተደርጎላቸዋል።

## በኤች አይ ቪ ኤድስ

እንደሚታወቀው በኤች.አይ. ቪ የሚደርሰው ችግር ድሮ የጤና ችግር ተደርጎ ይወሰድ ስለነበር የአለማያ ፕሮጀክት ሲቀረፅ ብዙም ትኩረት አልተሰጠውም። ስለሆነም ሰልፍ ሄልፕ ዲቨሎፕመንት ኢንተርናሽናል በ2004 ትኩረት በመስጠት በመከሄድ ባለው ፕሮጀክቶች ጋር በጥምረት የሚሰራ "mainstreaming HIV/AIDS" በሚል የ3 ዓመት ፕሮጀክት ቀርጾ እየተገበረ ይገኛል። ይህ ፕሮጀክት ለብቻው የሚሰራ ሳይሆን በአለማያ ፕሮጀክት በሚከናወኑት የተለያዩ የልማትና የማህበራዊ አገልግሎት ስራዎች ጋር በማቀናጀት ነው።

የበሽታው ስርጭት ወደ ገጠሩ ህብረተሰብ እንዳይስፋፋ በማለት ለተለያዩ የህብረተሰብ አባላት የግንዛቤ ማስጨበጥ ውይይቶች ተከሄደዋል። በግንዛቤ ማስጨበጫ ላይ የተሳተፉት የህብረተሰብ ክፍሎች፣ አርሶ አደሮች፣ የትምህርት ቤት ማህበረሰብ እንዲሁም የሃይማኖት አባቶችና የእድር መሪዎች ይገኙበታል።



School anti-HIV/AIDS clubs competition

ይህም የግንዛቤ ማስጨበጫ ውይይቶች ለማከሄድ ስልጠና አስፈላጊ ስለሆነ ለ32 መምህራን፣ ለ100 የአርሶ አደር ተወከዮች እና 28 የእምነትና የእድር መሪዎችን ለህብረተሰቡ ትምህርት ለመስጠት እንዲቻል ስልጠና ተሰጥቶቻቸዋል።

በሌላው በኩል 100 ለሚሆኑ የልማት ጣቢያ ሰራተኞች (mainstreaming of HIV/AIDS with Agricultural sector) በሚለው ስልጠና ላይ ተሳትፈው ሁሉም በየቀበሌያችው የተለያዩ ስዎችን በመስጠት ላይ ናቸው። እነዚህን የልማት ሰራተኞች ከስልጠናው በተጨማሪ ለሚሰሩት ሥራ እንዲረዳቸው ማኑዋል ተዘጋጅቶ ተሰጥተቸዋል። እንዲሁም በሚሰራውን ስራ ዙሪያ የተለያዩ ውይይቶችን በማዘጋጀት ውይይት እየተደረገ ነው።

የፕረጀክቱ ሰራተኞች የ "mainstreaming" ፅንስ ሃሳብ ስልጠና ወስደው በሚሰሩት የተለያዩ የፕሮጀክቱ ኮምፖነቶች ጋር በማቀናጀት የተለያዩ ስራዎችን በመስራት ላይ የገኛል። ለወደፊቱ ደግሞ ፕሮጀክቱ እነዚህን ሥራዎች በሰፊው ለመቀጠል እና የጋንዛቤ ማስጨበጫ ውይይት በተጠናከረ ሁኔታ ለመስጠት (community capacity enhancement) ስልጠና ለመስጠት በዝግጅት ላይ ይገኛል።

